# ቅማንት

## አረማዊ-ኦሪታዊ ኢትዮጵያዊ ገበሬ

ፕሮፌሰር ሲ ጋምስት እንደጻፈው

ትርጉም፡ ባዩ ቦጋለ ላቀው

# ቅማንት

## አረማዊ-አሪታዊ ኢትዮጵያዊ ገበሬ

ፕሮፌሰር ፍሬደሪክ ሲ ጋምስት እንደጻፈው

## ትርጉም፦ ባዩ ቦጋለ ላቀው



# የቅማንት ሕብረተሰብ አሠፋፈር

37°
37°30'
ጓዋንግ ወንዝ
ካች
ፈንቀራ
ትክል ድንጋይ
ባጅና
ቀላጅ
ኮሶዬ
ጨጨቅ
ሳቫራ
ኩሰዩና
ጎርጎር
ጋላገር
ጭላ
ጎንደር
ጋቫ
ቀሬ ዳቫ
አይከል
አዘዞ
አምቦበር
ሳራቫ
ተንከል
12° 30'
መገጭ ወንዝ
ሰሜን
ጉርጉራ
37°
37° 30'
ጣና ሐይቅ

ጠጠር መንገድ
ዋና የገጠር መንገድ
አነስተኛ የገጠር መንገድ
ቅማንቶች የማይኖሩበት አካባቢ



# ደራሲውና መጽሐፉ

## ደራሲው

ፍሬድሪክ ሲ. ጋምስት በማስቹሴትስ ዩኒቨርሲቲ የአንትሮፖሎጅ ፕሮፌሰር ሲሆኑ ሎሳንጀለስ በሚገኘው በካሊፎርኒያ ዩኒቨርስቲ በከፍተኛ ማዕረግ የመጀመሪያ ድግሪያቸውን፣ ቤከርሊይ በሚገኘው በዚሁ ዩኒቨርሲቲ የፒ:ኤችዲ ዲግሪያቸውን አግኝተዋል:: በኢትዮጵያ ካደረጉት የመስክ ጥናቶች በተጨማሪ በአሜሪካ ስለባቡር ሠራተኞች ሰፊ ጥናቶችን አከናውነዋል::

## ስለመጽሐፉ

ይህ ጥናት በምዕራብውያን ተማሪዎች ዘንድ ብዙ ስለማይታወቅ ስለ አንድ ጥንታዊ ኢትዮጵያዊ ባህል ነው:: የቅማንት ሕዝብ ኩሼቲያንና የኩሽቲክ ቋንቋ የሚናገር፣ ሃይማኖቱ አረማዊ-አሪታዊ በአብዛኛው ሆኖ በመጠኑም ቢሆን አንዳንድ የክርስትና እምነቶችን ያካተተ ነው:: የምዕራብያውያን ሃይማኖቶች በየጊዜው ለውጥ ሲታይ ሃይማኖታቸው ላለፉት ሁለት ሺህ ዓመታት ምንም ለውጥ ሳይታይበት ቆይቷል:: የሰሜንና የመካከለኛው ኢትዮጵያ የመጀመሪያ ሠፋሪዎች አገዎች ሲሆኑ፣ ቅማንት የአገው አንዱ ቅርንጫፍ ነው:: የእስልምና ሃይማኖት ከመምጣቱ በፊት የቅማንት ባህል የክርስትና ሃይማኖት ተፅዕኖ ቢኖርበትም ጥንታዊ የእብራውያን ሃይማኖት የሆነውን የአሪት እምነቶችን ለዘመናት ይዞ በመቆየቱ በምዕራባውያን የባህል ታሪክ ጥናት ልዩ ትኩረት ሊሰጠው የሚገባ ነው::

የቅማንት አርሶ አደሮች በአውሮጳና በአሜሪካ ዘመናዊ ሥልጣኔ ሳይለወጡ በውስጥ ተፅእኖ ባህሉ እንዴት እንደተለወጠ የሥነ ሕዝብ ተመራማሪዎች (አንትሮፖሎጅስትን) ልዩ ትኩረት የሚስብ ሆኗል:: በሌሎች ሕብረተሰቦች እንደደረሰው ሁሉ የምዕራባውያን ሥልጣኔ ባይወረስም በኢትዮጵያ የአማራው ሕዝብ ወሳኝ የሆነ ተፅእኖ ስላደረሰበት የአማራ ባህልን በመቀበል አማራ (አማሃራይዝድ) እየሆነ መጥቷል:: ይህ ሁኔታ የተጀመረው በ13ኛው መቶ ክፍለዘመን መሆኑ ቢታወቅም የባህላቸውና

የሃይማኖታቸው ሥርዓት ከሌላው ሕዝብ ጋር እንዳይገናኙ አጥር ሆኖ በመቆጣጠሩ እስካሁን ሙሉ በሙሉ ሳይዋሃዱ ቆይተዋል።

ዶክተር ጋምስት ለምዕራባዊው ዓለም የባህል ታሪክ ጥናት ተመራማሪዎችና በዓለም ስላሉት ባሕሎች ጥናት ፍላጉት ላላቸው የሥነ ሕዝብ ተመራማሪዎች ሁሉ ጠቃሚ ጥናት አቅርበዋል። ደራሲው እራሳቸው በሥነሥርዓቶች ላይ ተካፋይ በመሆንና በቅርብ ከጉዳዩ ጋር ግንኙነት ያላቸውን ግለሰቦችን ኑሮ በመከታተል ገለልተኛ አቋም በመያዝ ያቀረቡት ጥናታዊ ጽሑፍ ስለቅማንት ባህል ግልፅ የሆነ ግንዛቤ እንዲኖረን እንደሚያደርግ እሙን ነው።

ጆርጅና ሉዊስ ስፒንደር



# መቅድም

«ቅማንት፣ አረማዊ-ኦሪታዊ ኢትዮጵያዊ ገበሬ» የተሰኘው ይህ መጽሐፍ በጐንደር ከተማ ዙሪያ ስለሚገኘው የአገው ሕዝብ ቅርንጫፍ አንዱ ስለሆነው ስለቅማንት ኅብረተሰብ ባህልና ታሪክ በሰፊው ያስረዳል:: መጽሐፉ በመስክ ጥናት ላይ ተመስርቶ ከአርባ በላይ የሚሆኑ መጻሕፍትን በማገናዘብ በፕሮፌሰር ፍሬደሪክ ሲ ጋምስት "The Qemant, A Pagan - Hebraic Peasantry of Ethiopia" በሚል ርዕስ እ.ኤ.አ. በነሐሴ ወር 1969 ዓ.ም. ከተጻፈው መጽሐፍ የተተረጐመ ነው:: ስለ ቅማንት ሕዝብ ካሁን በፊት ከተጻፉት መጽሐፍትም ሆነ አጫጭር ሥነጽሑፎች የበለጠ በተሟላ መልክ ሚዛናዊነትን ጠብቆ የተዘጋጀ በመሆኑ በተለይ ስለዚህ ሕዝብና በአጠቃላይ ደግሞ ጐረቤቱ ስለሆኑት በሰሜናዊ-ምዕራብ ኢትዮጵያ ጥንታዊ ሕዝቦች አሠፋፈር፣ ባሕልና ታሪክ ግንዛቤ ለማግኘት ጠቃሚ መሆኑን ለመግለጽ እወዳለሁ:: ምንም እንኳን መጽሐፉ ከተጻፈ ወዲህ ቅማንትን ጨምሮ በአጠቃላይ በኢትዮጵያ ሕዝቦች ላይ ከፍተኛ ለውጦች የተከሰቱ መሆኑ ባይካድም የመጽሐፉ የባሕልና የታሪክ መዘክርነቱ ሕያው እንደሆነ ይቆያል::

የመስክ ጥናቱ የተካሄደው እንደ እ.ኤ.አ. ከ1964 ዓ.ም ጀምሮ ለአሥራ አራት ወራት ያህል በጐንደር አካባቢ በሚገኙ የቅማንት ማዕከል በነበሩት በከርከርና በጭልጋ ከአርባ በላይ የሚሆኑ ኅብረተሰቦችን ያካትታል፡ ከዚህም በስተቀር በቤጌምድርና ሰሜን ተበታትነው የነበሩትን የአገው ቅርንጫፍ የሆኑትን ፈላሻዎችንና፣ በጎጃም የሚገኙትን አዊያን፣ እንዲሁም በጣና ኃይቅ አካባቢ ያሉትን ወይጦዎችን ጥናቱ ሳይዳስስ አልቀረም፡ ስለቅማንት ሕዝብ ባሕልና ታሪክ በተቻለ መጠን ተሟልቶ የቀረበውን ይህን ጥናታዊ ጽሑፍ በማቅረባቸው ለደራሲው ያለኝን አክብሮት በዚህ አጋጣሚ እገልጻለሁ::

ይህ መፅሐፍ ለሕትመት እንዲበቃ በሃሣብም ሆነ በማንኛውም ረገድ የረዱኝን በውጭ አገር የሚኖሩትን ወንድሜን አቶ ዘውዱ ቦጋለንና ከእሳቸው ጋር በመሆን ከልብ የተባበሩኝን አቶ ነጋሲ ታፈረንና አቶ ፀጋ ጣሰውን፣ እንዲሁም ሌሎቹን ወንድሞቼንና እኅቶቼን በመጀመሪያ ደረጃ ከልብ አመሰግናቸዋለሁ::

ያላቸውን ውስን ጊዜ መስዋዕት አድርገው ረቂቁን በማንበብና አስፈላጊውን የቋንቋ እርማት በማድረግ የረዱኝን ጓደኛዬን መምህር ሀብተሥላሴ ደምሴንና ስለመጽሐፉ የበኩላቸውን ምክር የለገሡኝን በአዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ የሳይኮሎጅ ረዳት ፕሮፌሰር ዶክተር ተካ ዘውዴን ሳላመሰግን አላልፍም። ከዚህም በተጨማሪ በመጽሐፉ ቅንብር በኩል የቴክኒክ ድጋፍና ምክር የሰጡኝን የኢተርናሽናል የልማት አማካሪ ድርጅት ዋና ሥራ አስኪያጅ ዶክተር ዳኘው እሸቴንና የእጅ ጽሁፉን በኮምፒውተር በመጻፍ የረዳችኝን ፀሐፊያቸውን ወይዘሪት ትሬዛ ባዩን ከልብ አመሰግናለሁ።

ባዩ ቦጋለ ላቀው
አዲስ አበባ
1993

# ማውጫ

ገፅ

# ምዕራፍ አንድ

## መግቢያ

የመጀመሪያዎቹ የሰሜንና የመካከለኛው ኢትዮጵያ ሠፋሪዎችና የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪ የአገው ሕዝብ አካል የሆነው የቅማንት ሕዝብ ብዛቱ ከ20,000 እስከ 25,000 ይደርሳል:: የቅማንት መሬት ተብሎ የሚታወቀው የሚገኘው በደጋው ሰሜናዊ ኢትዮጵያ ከአባይ ወንዝ መነሻ ከሆነው ከጣና ኃይቅ በስተሰሜን ከብዙ መቶ ዓመታት በፊት የጥንታዊ ኢትዮጵያ ዋና ከተማ በነበረችው በጐንደር ከተማ ዙሪያ ተከልሎ ሲሆን፣ የአየሩ ጠባይ ወይና ደጋ ነው::

የቅማንት ሕዝብ በመንደሮች በአንድ ላይ ተሰብስቦ የሚኖር አይደለም:: ግድግዳቸው ጨፈቃ ሆኖ በጭቃ የተመረገ፣ ጣሪያቸው ክብና ባለጉልላት የሣር ቤቶች ከአገሩ ዳር እስከዳር በግጦሽና በእርሻ ቦታዎች ላይ ተበታትነው ይገኛሉ:: በአንድ አካባቢ ከአንድ እስከ አራት የሚሆኑ መኖሪያ ቤቶች ተበታ ትነው የሚገኙ ቢሆንም ሕብረተሰቡ በማኅበራዊ ኑሮው በቅርብ የተሳሰረ ነው::

## መሬቱ

የቅማንት አገር የመሬት ዕይታ በየወቅቱ ተለዋዋጭ ነው:: በዝናብ አዘል ደመና ሰማዩ በሚሸፈንበት በክረምቱ ወራት ያገሩ አካባቢ ደብዛዛ ሆኖ መሬቱ ረግረጋማና ወንዞቹ አፈሩን በመሸርሸር በጣም ደፍርሰው በአደገኛ ሁኔታ ሲደነፉ ማየት የተለመደ ነው:: ከክረምቱ ወቅት ቀጥሎ የታረሱት መሬቶች ሁሉ በሰብል ስለሚሸፈኑ አካባቢው በሙሉ ወደ አረንጓዴነት ይለወጣል:: በደብዛዛ ሰማያዊ የኑግ አበባዎችና ደማቅ ብጫ አደይ አበባዎች በለምለም ሣር ታጅበውና ተሸፍነው የሚታዩት ጋራዎች ዓይንን ይማርካሉ:: በበጋ ወቅት ደግሞ ወንዞች እንደኩል በጠራ ውሃ ይሞላሉ::

የበጋው ወቅት እየተቃረበ ሲመጣ መሬቱ ይደርቃል፡ ወንዞችም ይጐድላሉ፣ ሰብሎችም ሲጐመሩ አካባቢው ቢጫማ

ወርቅ በሆነ ሕብረቀለም አሸብርቆ ይታያል። በስፋት ተንሠራፍተው የላይ መደባቸው በክፍት ቀይ ወይም በነጭ አበባ ያጌጡት የግራር ዛፎች በደማቅ ሰማያዊ ጠፈር ተከልለው የሚታዩበት ወቅት ነው። ዘግየት ብሎ በበጋው ወቅት ሰብሉ ሲሰበሰብ የእርሻ መሬቶች ባዶ ደረቅና ወደ ቢጫማነት ተለውጠው የግጦሽ ሣር ብቻ ይታያል። ወንዞች ደርቀው አልፎ አልፎ ሳይደርቁ የቆዩት የወንዝ ኩሬዎች ደግሞ እንደገና ጉዞአቸውን ወደ ጣና ኃይቅ ለመቀጠል በጉጉት የሚጠባበቁ ይመስላሉ።

ከቅማንት አገርና ከሌሎች አካባቢዎች በሚወርዱ ድፍርስ ወንዞች የሚመገበው የጣና ኃይቅ፣ ውሃው ሞልቶ ተርፎ ለም አፈር በመሸከም ከሚወርደው ከአባይ ወንዝ ጋር በመዳበል የአንድ ማይል ጥልቀት ያለውን ሸለቆ በመሰንጠቅ አባይ እየተምዘገዘገና እየስገመገመ ወርዶ ከነጭ አባይ ጋር በመቀላቀል በረሃማውን የሱዳንና የግብፅን መሬት ከረዥም ጉዞ በኋላ አቋርጦ ወደ ሜዲተራንያን ባሕር ይገባል።

የቅማንት መሬት ለም ቢሆንም ገበሬው የሚኖረው ከእጅ ወደ አፍ ነው። ኢኮኖሚው የተመሠረተው በግብርና ላይ እንደመሆኑ ሞፈርና ቀንበር በእርሻ በሬዎች በመጠቀም በማረስ ከሚገኘው ምርት በተጨማሪ ከብት በማርባት ኑሮአቸውን ይደጉማሉ። እህል፣ ጥራጥሬ፣ የቅባት እህልና ለምግብነት የማያገለግሉ ከሥራ-ሥር የሚገኙ ሰብሎች የኢኮኖሚያቸው አውታር ሲሆኑ፣ እንዲያውም አንዳንዶቹን የሰብል ዘሮች ጥንት ከአምስት ሺህ ዓምታት በፊት የቅማንት ጥንታዊ ትውልዶቻቸው ለመጀመሪያ ጊዜ ያላመዷ ቸውና ሲጠቀሙባቸው የቆዩ ናቸው።

## ቅማንት ገበሬ ነው?

ቅማንቶች አርሶ አደሮች ናቸው። ይህንን ሊያስኝ ያስቻለው እርሻ እያረሱ ከሚያመርቱት የሚተርፋቸውን በገበያ ላይ በመሸጥ ግብር በመክፈል ከላይ እስከ ታች ለተዘረጋው የኢትዮጵያ የአስተዳደር መዋቅር እንዲንቀሳቀስ አስተዋጽኦ ስለሚያደርጉ ነው። የኢትዮጵያ ሥልጣኔ በሚዲተራንያንና በቅርብ ምሥራቅ አካባቢ በቅድመ ኢንዱስትሪ ዘመን ከስድስት ሺህ ዓመት በፊት በምዕራብ እስያ የእርሻ አብዮት ከተከሰተ በኋላ ወደ ደቡብ ቀስ በቀስ እየተስፋፋ የመጣው የሥልጣኔ ተቀጽላ

አካል ነው። ነገር ግን ይህ ዓይነት ሥልጣኔ ወደ ኢትዮጵያ ሊስፋፋ የቻለው ከሦስት ሺህ ዓመት በፊት ትንሽ ቀደም ብሎ እንደሆነ ይታወቃል።

በዚህና በሌሎች ምክንያቶች የቅማንት ሥልጣኔ እኛ ካለን ዘመናዊ የኢንዱስትሪያል ከተማ ሥልጣኔ አስቀድሞ የነበረውን የኀብረ ተሰብ ሥልጣኔ የሚወክል ነው። ቅማንትን ማጥናት ማለት ብዙ ጥናት ያልተካሄደበትንና ባልታወቀችው ኢትዮጵያ የተካሄደውን የባህል ለውጥ ሂደት እንድናውቅ የሚረዳን ከመሆኑም በላይ በመካከለኛው ምሥራቅና በሰሜን አፍሪካ የእስልምና ሃይማኖት ከመምጣቱ በፊት የነበረው የክርስቲያን ሥልጣኔ ሳይጠፋ የቆየበትን ብቸኛ አካባቢ ለማወቅ የሚያስችለን ይሆናል። ከሁሉም በላይ ደግሞ ቅማንትን ማጥናት ማለት ከብዙዎቹ ኀብረተሰቦች መካከል አነስተኛ አርሶ አደሮች በሚካሄደው ዓለም አቀፍ ዘመናዊ ሥልጣኔና የኢንዱስ ትሪዎች እድገት ተፅዕኖ ሳይለውጣቸው እንዴት እንደቆዩ ለማወቅ ይረዳናል። አሁንም ቢሆን ቅማንት ጉልህ የሆነ የባህል ለውጥ እያደረገ መሆኑ ቢታወቅም ለውጡ የምዕራባውያንን የባህል ፍሙና የተከተለ ሳይሆን በአካባቢያቸው የሚኖረው የአማራ ገበሬ የባህል ለውጥ ሂደቶችን የተከተለ ነው።

የቅድመ ኢንዱስትሪ ሥልጣኔ ማኀበራዊ ኑሮ የበለጠ ውስብስብና በቴክኖሎጂ ኋላቀር ከሆኑት አዳኞች፣ ፍራፍሬ ለቃሚ ዎችና በኅሮ እርሻ ከሚተዳደሩት ማኀበረሰብ በጣም የላቀ ነው። የከተሞች መቆርቆር፣ የሥነ-ጽሑፍ ማቆጥቆጥ በማረሻ ማረስ፣ ብረት ማቅለጥ፣ የመታሰቢያ ሕንፃዎች መገንባት ዓይነተኛ መገለጫዎች ሲሆኑ፣ ቢያንስ ሁለት የኀብረተሰብ መደቦች ይኖሩታል። የኀብረ ተሰብ መደቦች ይኖራሉ ስንል በአንድ በኩል "ታላቅ ባሕል" ያለው ኀብረተሰብ የተባለው ባህሉ ያደገውና የነቃው በከተማ ነዋሪ የሆነው ክፍል ሲሆን ሌላው ደግሞ "አነስተኛ ባህል" ያለው ገጠሬውን አርሶ አደር የእጅ ሙያተኛውን ወይም በሂደት "በታለቁ ባህል" ሊታቀፉ ያልቻሉትን የከተማ ነዋሪዎችን ያጠቃልላል።

በፖለቲካ የተደራጀ ሥልጣኔ ወደ መንግሥት ወይም መንግሥታት በሚለወጥበት ወቅት ሥልጣን የያዘውና የነቃው ክፍል ሌሎች ያልነቁትን እንደገበሬው ያሉትን ኀብረተሰቦች

ተቆጣጥሮ ይመራል፡ ያስተዳድራል። በአፀፋው ደግሞ ገበሬው ከሠብሉና ከጉልበቱ ለገዥው መደብ ማበርከት ግዴታ አለበት።

በፖለቲካው በኩል ቅማንት ባለፉት ስድስት መቶ ዓመታት የራሳቸው የሆነ የገበሬ መደብ ባላቸው በአማራውና በትግሬው የገዥ መደብ ሥር ሲተዳደር ቢቆይም በማይናቅ ደረጃ የራሱ የሆነ የውስጥ የፖለቲካ ነፃነት ነበረው። ይህም በመሆኑ የራሱ የሆነ በተለያዩ እርከን የተደራጁ የሃይማኖትና የፖለቲካ ሥርዓት ይዞ እስከ ፲፱ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ሳይለወጥ ቆይቷል። አሁንም ቢሆን ይኸው ሥርዓት በተመናመነ መልኩ ተጥሏል። ቅማንትን አንድ ላይ አስተሳስሮና አቀራርቦ ያቆየው ሥርዓት በሦስት እርከን የተከፈለ ነው። በቅደም ተከተል ለመግለጽ ያህል የመጀመሪያው በዝቅተኛ ደረጃ የሚገኘው የአባውንቶች ሸንጎ፣ በመካከለኛ ደረጃ የሚገኘው ከፍተኛና ዝቅተኛ ቀሳውስት ስብስብ እና በመጨረሻ ደግሞ ቁንጮው ላይ የሚገኘው የሃይማኖትና የፖለቲካ የበላይ የሆነው «ወምበር» ናቸው። በከፍተኛ ደረጃ የሚገኘው ወምበሩ የአማራውን ባላባታዊ አስተዳደር የበላይነት ይቀበላል። በክርስቲያኒቱ ኢትዮጵያ የነበረው ባላባታዊ ሥርዓት በምንም ዓይነት ሳይለወጥ እስካሁን የቆየ ሲሆን በክርስቲያን አውሮጳ ተንሠራፍቶ ከቆየው ባላባታዊ (ፊውዳል) ሥርዓት ተመሳሳይነት ያለው ነው።

## የኅብረተሰቡ ትስስር ምክንያቶች

የቅማንት መኖሪያ ቤቶች ተበታትነው የሚገኙ ቢሆንም የእነሱ ብቻ የሆነው ልዩ የፖለቲካ ሥርዓትና ከቤተሰብ አልፎ ከሌሎች ኅብረተሰብ ጋር ያላቸው የጠበቀ ግንኙነትና ዝምድና ሁሉም በአንድ ላይ ተሳስረውና ተቀራርበው እንዲኖሩ አድርጕአቸዋል። የእያንዳንዱ ቤተሰብ የአባትን የዘር ሐረግ ተከትሎ የሚደረገው የዘር ቆጠራ ወደላይ እየተራዘመ ሄዶ የዋናው የዘር ግንዳቸውና አንዱን ከሌላው ጋር በመጨረሻ ከሚያገናኛቸው የጐሣ መሥራች ከሆነው ባህላዊ ጀግና አባት ላይ ይደርሳል። የቅማንት ጐሣዎች ልዩ ልዩ ሐረግና ዘሮቹ ሲኖሩ ዋቸው ወደላይ እየወጣ ሲሄድ ከሁለት ታላላቅ የዘር ክፋዮች (ቡድኖች) ላይ ያርፋል። ይህም መሠረታዊ የሆነ ማኅበራዊ የጐሣ ኅብረተሰብ እንዲመሠረት ምክንያት ሆኖአል። ሁሉም ቅማንት ከአንደኛው የዘር ክፋይ ላይ ብቻ ስለሚደርስ በጋብቻ ሕጋቸው መሠረት አንዱ ከሌላው የዘር ሐረግ ጋር ሊጋባ ይችላል።

የቅማንት ሃይማኖት ጥንታዊና ልዩ ልዩ ዕምነቶችን ያካተተ ሃይማኖት በመሆኑ የተለየና ትኩረትን የሚስብ ነው:: በሰሜን ማዕከላዊ ኢትዮጵያ የእስልምና ሃይማኖት ከመምጣቱ በፊት በቅደም ተከተል የተከሰቱ ሦስት ዓይነት ሃይማኖቶች ነበሩ:: ከሁሉም በጣም ጥንታዊ የሆነው የጥንት አገዎች በተለያየ መልክ ያመልኩት የነበረውና እስከቅርብ ጊዜም የአሁኖቹ የአገው ሕዝቦች ያምኑበት የነበረው አረማዊ-አገው እየተባለ የሚታወቀው ነው:: ሁለተኛው ደግሞ ከሁለት ሺ ዓመት በፊት በሰሜን ኢትዮጵያ የተሠራጨው የእብራውያን ሃይማኖት (ኦሪት ) ሲሆን፣ ሦስተኛው ደግሞ ከቅርብ ጊዜ ጀምሮ ማለትም ከአንድ ሺህ ስድስት መቶ ዓመት በፊት የተስፋፋው የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ክርስቲያን ሃይማኖት ነው:: የክርስትናን ሃይማኖት ከኢትዮጵያ ሕዝቦች አንድ ሦስተኛው ያመልከዋል::

የቅማንት ሃይማኖት በአብዛኛው አረማዊ-አገው ሲሆን በተጨማሪም የእብራዊ (ኦሪት) ሃይማኖት እምነትን በውስጡ ያቀፈና በመጠኑም ቢሆን አንዳንድ የክርስቲያን እምነቶችን ያካተተ ነው:: በመሆኑም የቅማንት ሃይማኖት አረማዊ−ኦሪታዊ ነው እንላለን:: በቅማንት ሃይማኖት ያለው የኦሪት እምነት ይዘት ባለፉት ሁለት ሺ ዓመታት የእብራውያን ሃይማኖት እየተለዋወጠ ና እየተሻሻለ የመጣ ቢሆንም እስካሁን ሳይለወጥ ጥንታዊነቱን እንደያዘ ይገኛል:: የቅማንት ጐረቤት የሆነው በአገውነቱ የሚታወቀው «የኢትዮጵያ ጥቁር እስራኤላዊ» እየተባለ የሚታወቀው ፈላሻ ሲሆን ከፍ ብሎ የተገለፀውን ዓይነት የኦሪት ሃይማኖት አምላኪ ነው::

ምንም እንኳን ፈላሻዎች በአንድ አምላክ ብቻ ነው የሚያምኑት ቢባልም በሂደት ከሌሎች እምነቶች ወስደው ወደ ራሳቸው ሃይማኖት ያዋሃዷቸው እንዳሉ ስለምንረዳ የፈላሻን ሃይማኖት ሙሉ በሙሉ ኦሪታዊ ነው ለማለት ስለማያስደፍር አረማዊ-ኦሪት ነው የምንለው::

## የቅርብ ግንኙነት

ኦሪት መቶ ሃምሣ ሺ እስኩዌር ማይል ስፋት ያላት ኢትዮጵያ በጠቅላላ ከሰባ በላይ የቋንቋ ዓይነት የሚናገሩ በግምት ከሃያ ሁለት ሚሊዮን ሕዝብ በላይ የሚኖርባት አገር ስትሆን፣

የቅማንት ሕዝብ ከሌሎቹ ጐረቤት ከሆኑት ሕዝቦች ጋር ያለውን ግንኙነት መመልከት አስፈላጊ ይሆናል። ጥናቱ የተካሄደው ጥንት የሀበሾች ሀገር (አቢሲኒያ) እየተባለ ይጠራ በነበረው በሰሜን እና በማዕከላዊ ሰሜን ደጋማው የኢትዮጵያ ክፍል ነው። ይህ አካባቢ ሀበሾች እየተባሉ የሚታወቁ የሦስት ዋና ብሔረሰቦች መኖሪያ ነው። ለመግለጽም ያህል የፖለቲካውን የበላይነት የያዘው ቁጥሩ እስከ 5,000,000 የሚደርሰው አማራ፣ ከአማራው ጋር የሚዛመደው የፖለቲካውን መድረክ የሚጋራው ቁጥሩ 1,500,000 የሚሆነው ትግሬ እና ጥንታዊና የመጀመሪያው የአብዛኛው የአገር ክፍል ሠፋሪዎች የነበሩት በአሁኑ ጊዜ ቁጥራቸው ተመናምኖ 250,000 የሚደርሰው የአገው ሕዝብ ሲሆን ቅማንት የአገው አንዱ ቅርንጫፍ ነው። እነዚህ ሦስት ሕዝቦች ምንም እንኳን የመጀመሪያዎቹ ሁለቱ ሴማዊ ቋንቋ ተናጋሪ፣ ሦስተኛው ደግሞ በመሠረቱ የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪ ቢሆኑም ሁሉም ዘርያቸው አንድ ሆኖ የጋራ የሆነ የባህል ሥረ-መሠረት ያላቸው ናቸው። በነገራችን ላይ ከአፍሮ -እስያ አምስት የቋንቋ ንዑስ ዘሮች ሁለቱ የሴምና የኩሽ ቋንቋዎች መሆናቸው መታወቅ አለበት።

ዝርያን በተመለከተ አብዛኛው ኢትዮጵያዊ ኮኬዝያን ሆኖ ሴማዊም ሆኑ የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪዎች አንድ ዓይነት የሰውነት ይዘትና ቅርጽ አላቸው። በርግጥ ከጥቁር ዝርያዎች (ቡሽማኖይድስ) ጋር በመጠኑ የመዳቀል ሁኔታ ቢኖርም የኢትዮጵያ ውያኑን መሠረታዊ የሆነውን መልክና አቋም አለወጠ ውም። የኮኬዥያን ዝርያ ያላቸው ኢትዮጵያውያን ቀጥ ያለ፣ መካከለኛ ቁመናና ደልደል ያለ ሰውነት አላቸው። መልካቸውን በተመለከተ አንዳንዶቹ ጠየም ያሉ፣ ሌሎቹ ደግሞ የቀይ ዳማና ቀዮች ናቸው። የራስ ቅላቸው በአብዛኛው ሾጠጥ ያለ ሆኖ አፍንጫቸው በከፊል ሠፋፊና አንዳንዱም ቀጥ ያለ ነው። ፀጉራቸው አንዳንዱ ዞማ፣ ሌሎች ደግሞ ከርዳዳ ፀጉር ያላቸው ይገኛሉ።

አገው፣ አማራና ትግሬ ከደጋው ምስራቃዊ ቆላማ አገር ከሚኖሩት ጥቁሮች ዘር የበላይ ነን ብለው የሚያምኑ በመሆኑ ከእነሱ ጋር ባይጋቡም በአገልጋይነት ከያዙአቸው ጥቁሮች ልጅ ማስወለድ ግን የተለመደ ነበር። አማራና አገው ከእነሱ አፈጣጠ

ርና መልክ ለየት ያሉትን ሰዎች በሚከተለው አፈ-ታሪክ ለይተው ያስቀምጣሉ።

> «እግዚአብሔር ሰውን በሚፈጥርበት ወቅት የሰው ምስል ሸክላ አፈር ከሠራ በኋላ በእሳት ኢቃጥሎት በጣም አረረበትና ጥቁር ሰው ተፈጠረ። እንደገና እግዚአብሔር ሌላ ምስል ሠርቶ በእሳት ለትንሽ ጊዜ ለብልቦ ሲያወጣው ሊጥ የመሰለ ነጭ ሰው ሆነበት። በመጨረሻም ሌላ የሰው ምስል ለሦስተኛ ጊዜ ሠርቶ በአማካይ ደረጃ ተኩሶ አወጣው። በዚህም መሠረት ወርቃማ ቡና መልክ ያለውን ሰው ፈጠረ። ይህ ነው ትክክለኛውና ኢትዮጵያዊው ሰው ብሎ በመቀበል እግዚአብሔር የሰው ፈጠራ ሥራውን አጠናቀቀ» የሚል አፈ–ታሪክ አሁንም እየተናገረ ነው።

የኢትዮጵያ ሴማዊ ቋንቋ ተናጋሪዎች ከ1,500 ዓመታት ወዲህ በሚገባ በማስረጃ ተደግፎ የተጻፈ ታሪክ ሲኖራቸው ከዚያ ወደኋላም ሌላ 1,500 ዓመታት ቀደም ብሎ በሚገባ በማስረጃ ባይረጋገጥም በአፈ-ታሪክ የተደገፈ ታሪክ እንዳላቸው ለመረዳት ተችሏል። እንደ አገው ስላሉት የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪ ሕዝቦች ግን የማኅበራዊና የኢኮኖሚያዊ እድገታቸው ብዙም አልተዘገበም።

በማዕከላዊ ሰሜን ኢትዮጵያ በሰፊው ተሰራጭተው የነበሩት የአገው ቅርንጫፎች ስምንት ናቸው። ስባቱ፡- ቅማንት፣ አዊያ፣ ኩምፈል፣ አሚር፣ ቢለን፣ ዳሞት እና ሀምታ በአንዳንድ በተወሰኑ አካባቢዎች የሚገኙ ሲሆን ስምንተኛው ፈላሻ የሚባለው የአገው አንዱ ቅርንጫፍ ግን በአማራው መካከል ተበታትኖ የሚገኝ ኅብረተሰብ ነው። ሁሉም የአገው ቅርንጫፎች እርስ በእርሳቸው የሚግባቡበት ቋንቋ ወይም ደግሞ በአንዱ ጐሣ ብቻ የሚታወቅ የአካባቢያቸው ቋንቋ ሲኖራቸው በአብዛኛው ሁሉም አገዎች አማርኛ ወይም ትግርኛ መናገር ስለሚችሉ ሁለት ቋንቋ ተናጋሪዎች ናቸው። ዛሬ ሁሉም ቅማንት «ቅማንትኛ» የተባለውን የአካባቢያ ቸውን የአገው ቋንቋ መናገር አይችሉም። አንድ ሶስተኛው ቋንቋውን ጥሩ አድርገው ይናገራሉ፣ አንድ ሶስተኛው ስለቋንቋው ምንም ዕውቀት ስለሌላቸው አማርኛ ብቻ ይናገራሉ። ሌላው አንድ ሶስተኛው ደግሞ ሁለቱንም ቋንቋዎች በማደባለቅ የሚናገሩ ናቸው።

ምንም እንኳን ቅማንት የቋንቋው መለወጥና መዳከም ቢያጋጥመውም ከሌሎች ጉማዎች በተለየ መልክ የአገውን ባህል፣ የማኅበረሰብ ሥርዓትና አረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖትን



ስልሣ አምስት ዕድሜ ያስቆጠሩና የሦስት ትውልድ ቤተሰብ:: ብረት የሆነ ክንድ ያላቸው አዛውንት (በቀኝ በኩል) አገላብጠው ያርሳሉ፣ ባለቤታቸው በቀን ሃያ ኪሎ ሜትር ለውሃ ደርሶ መልስ ያደርጋሉ:: የጭቃና የጨፈቃውን ቤት ተመልከቱ::

ጠብቆ የቆዩ ኅብረተሰብ ነው:: ባህላቸው ከአማራውና ከትግሬው ባህል በጣም የተለየ በመሆኑ የቅማንትን ኅብረተሰብ እንዲጠና ምክንያት ሆኖኛል::

የቅማንት ሃይማኖት አረማዊ-አሪታዊ ሲሆን ሃይማኖታቸው ባህላቸው እንዳይለወጥ በአካባቢያቸው ካለው ጠንካራ ከሆነው የአማራው ባሕል ተፅዕኖ እንደ አጥር ሆኖ በመቆየቱ ልዩ የሆነውን ባህላቸውን ለዘመናት በመጠበቅ በማኅበራዊ ኑሮ ረገድ በከፊል ነፃ ሆነው መኖራቸውን እንገነዘባለን:: ይህ አረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖት ኅብረተሰቡ ከሌላው ጐሣ ጋር እንዳይገናኝ አግዶት እስከ 1880ዎቹ ቢቆይም፣ ከዚያ ዘመን ጀምሮ በግዳጅ የአማራን ባሕል እንዲቀበሉ በመደረጉ አጥር ሆኖ የቆየው የሃይማኖት ድንበር በመፍረሱ ባህሉ እየተለወጠና እየተመናመነ መጥቷል:: የባህል ለውጡ አሁንም የቀጠለ ሲሆን የሃይማኖቱም ተከታዮች ብዛት እየቀነሰ በመምጣቱ ከአረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖት ጋር ተሳስሮ የሚሄደው ማኅበራዊ ኑሮ በአማራው ባህል ተሸርሽሮ ይህ ልዩ ባህል ሊጠፋ ከመጨረሻው ደረጃ ላይ ደርሷል::

ለዘመናት ተፅዕኖዎቹን ሁሉ ተቋቁሞ ወደ አማራነት ሳይለወጥ እስከ አለፈው ምዕተ-ዓመት እንዴት እንደቆየ የረዱትን ሁኔታዎች በዚህ ጥናት ላይ እንመለከታለን:: በአሁኑ ወቅት አምስት መቶ ያህል አረማዊ-አሪታዊ ቅማንቶች አሉ:: በብዙ ሺዎች የሚቆጠሩት ግን ኦርቶዶክስ ክርስቲያን ቢሆኑም በእምነታቸው ውስጥ የጥንቱ ሃይማኖት ይዘት አልጠፋም:: በዚህ ጥናት ላይ የምናያቸው የጥንት ባህላዊ ይዘት በአሁኑ ጊዜ በቅማንት ባህል ባይታይም ይህ ሁኔታ ሊከሰት የቻለው ከመቼ ጀምሮ እንደሆነ ግምታዊ ጊዜ ለመስጠት ጥረት ይደረጋል::

ጥናቱ የቅማንትና አባቱ የሆነው የአገው ባህል ከጊዜ ወደጊዜ በምን ምክንያት እየተለዋወጠ እንደመጣ ይጠቁማል:: አንዳንድ የሰው ዘር ጥናት ምሁሮች የባህልን ለውጥ ሲያጠኑ አውሮጳውያን ከመምጣታቸው በፊት የባህል ለውጥ ሊኖር እንደማይችል አድርገው በዘልማድ ግምታዊ አስተያየት ይሰጣሉ:: ለመጥቀስም ያህል ሆመር በርኔት «የአውሮፓና የአሜሪካ ጣልቃ ገብነት ከጥንት ጀምሮ ሳይለወጥ የቆየውን የአገሬውን ሕብረተሰብ ባሕል አናጋው::» (1965.216 ):: ከዚህ ቀደም ብሎ ደግሞ ራልፍ ቢአልስ ሲጽፍ «የመስክና የቲዎሪ ጥናቶች በተለይ ስለባህል

በእንካ-በእንካ የለውጥ ጠባይ አውሮጳውያን በሌሉበት የተከሰተ ከሆነ ስለባህል ለውጡ ልዩ ትኩረት መስጠት ያስፈልጋል ይላል:: (1953 638 ) በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የባሕል ለውጥ ሂደትን ስናጠና ከጥንት ጀምሮ በኢትዮጵያ ባሉት የተለያዩ ሕዝቦች መካከል የባህል እንካ-በእንካ ልውውጥ እንደነበረ ለመገንዘብ ይቻላል:: ነገር ግን በኢትዮጵያ የባህል ለውጥ የአውሮጳ ባህል አነስተኛ ሚና እንኳን አልተጫወተም:: ስለዚህ ጉዳይ የአገውን የባህል ታሪክ በሚቀጥለው ምዕራፍ በምናይበት ጊዜ በዝርዝር እንመጣበታለን::

## ጥንታዊ ሀገር ጉብኝዎች

በ16ኛውና በ17ኛው መቶ ክፍለ ዘመናት የፖርቱጊዝ ቀሳውስት፣ ወታደሮችና ዲፕሎማቶች ኢትዮጵያን በጐበኙበት ጊዜ አንዳንድ ቁምነገሮችን ስለአገው ሕዝብ በጽሑፋቸው የጠቃቀሱ ቢሆንም በተለይ ስለ ቅማንት ሕዝብ ያነሡበት ጊዜ የለም:: በ18ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ነበር አውሮጳውያን ከጻፏቸው ጽሑፎች ስለቅማንት አንዳንድ ሁኔታዎችን ማወቅ የተጀመረው::

በማንባር ቀደም ሀብታምና በጣም ግዙፍ የሆነው የስኮትላንድ ተወላጅ ጀምስ ብሩስ ነበር አስደሳችና ተነባቢ በሆነው መጽሐፉ እ.ኤ.አ 1770 ዓ.ም ቅማንትን ከውጭው ዓለም ጋር ያስተዋወቀው:: «የአባይን ምንጭ ለማግኘት የተደረገ ጉዞ» በሚለው መጽሐፍ ስለኢትዮጵያ አምስት ቅፆችን የያዘ መጽሐፍ የጻፈ ሲሆን አንድ ገጽ ያህል ስለቅማንት ሲያትት «ቅማንት ከፈላሻ ጋር ተመሳሳይ የነበሩ.......» እና...... «ከፈላሾች ጋር አንድ ዓይነት ቋንቋ የሚናገሩ........» በማለት ጽፏል:: (1790፡4፡275):: ብሩስ በተጨማሪ ቅማንቶች በ1600ዎቹ ዓ.ም በአፄ ፋሲል ዘመን መንግሥት በክርስትና ሃይማኖት የተጠመቁ ቢሆኑም ክርስትናን አጥብቀው ስላልያዙ በወትሩ የራሳቸውን ጥንታዊ ባሕል ይዘው ይጓዙ እንደነበርና የክርስቲያን ባሕርይ የማያሳዩና ክርስቲያኖችን እንደረከሱ አድርገው ይመለከቱ እንደነበረ ይገልፃል:: (1790፡4፡275):: ቅማንቶች በዚያ ዘመን በክርስትና ሃይማኖት ተጠምቀው ነበር የተባለው የብሩስ አባባል ወደ ኢትዮጵያም በመጡ ሀገር ጎብኝዎች ያልተገለጸ በመሆኑ ትክክል ነው ብሎ ሙሉ በሙሉ ለመቀበል ያዳግታል:: በ1600ዎቹ ዓ.ም በክርስትና ሃይማኖት የተጠመቁ ቅማንቶች እንኳን ቢኖሩ ቁጥራቸው

እነስተኛና ምንአልባትም እሄ ሩሲል በአዲስ መልክ በቆረቆሯት ዋና ከተማቸው በጎንደር አካባቢ የሚኖሩት ሳይሆኑ አይቀርም።

ቀጥሎ ኢትዮጵያን የጎበኘው አውሮጳዊ ቄስ ሳሙኤል ጉባት «በአቢሲንያ የሦስት ዓመት ቆይታ» በሚለው መጽሐፉ እንደገለፀው ቅማንት በአንድ እግዚአብሔር እንደሚያምኑና ነገር ግን ስለሃይማኖታቸው ሲጠየቁ በቀልድ መልክ አሻሚ መልስ ይሰጣሉ ይላል። (1834፡364) ጉባት ከብሩስ የተለዩ ጠለቅ ያለ ጥናት ባይኖረውም ቅማንት የራሳቸው ቄስ እንደነበራቸው ይናገራል። በጉባትና ከብሩስ እንዲሁም ከሌሎች አውሮጳውያን ጽሑፎች ለመረዳት የተቻለው ቅማንቶች ሃይማኖታ ቸውን በሚስጢር እንደሚይዙና ማንም ወገናቸው ያልሆነና «የረከሰ» ሰው ስለዕምነ ታቸው እንዳያውቅ በንቃት ይከላከሉ እንደነበር ነው።

በ1830ዎቹ ዓ.ም. ኤድዋርድ ሩፔል የተባለ የጀርመን ተመራማሪ እንደጻፈው «ስለሃይማኖታቸው የተሟላ መረጃ ማግኘት አልተቻለም» ይላል። ሩፔል በተጨማሪ እንደገለጸው ቅማንቶች አረማዊ እንደነበሩ ነገር ግን ከሥረ-መሠረቱ አይሁዳዊያን /ጅውስ/ እንደነበሩና ቀደም ብሎ በነበሩት ምዕተ-ዓመታት በክርስቲያኖችና በኦሪት ሃይማኖት ተከታዮች በተካሄዱ ጦርነቶች ምክንያት የኦሪታዊ እምነታቸው እየቀነሰ መምጣቱን ያወሳል። (1840፣2፣148)። በተጨማሪም የቅማንት ሃይማኖት አረማዊ-ኦሪታዊ መሆኑን ገልጿል። ሩፔል እንደጠቆመው ቅማንት ኦሪታዊነቱ እየቀነሰ የመጣው ቀስ በቀስ ከጊዜ በኋላ መሆኑንና ለዘመናት በይበልጥ አረማዊ በመጠኑ ደግሞ ኦሪታዊ እንደነበረ ነው የምንገነዘበው። ይህ አገር ጉብኝ የቅማንት ሃይማኖት ምሥጢ ራዊ መሆኑን ባለመገንዘብ ቅማንቶች የተለዩ ዓመት በዓል እንደሌላቸውና ፆም እንደማይፆሙ አድርጐ አሳሳች የሆነ አስተያየት ሰጥቷል። በሀተታው ላይ አንድ የሕብረተሰቡ አባል ሲሞት ስለሚደረገው የቀብር ሥነሥርዓትና ስለጠላ ግብዣቸው ግን ሳይጠቅስ አላለፈም።

በመጠኑም ቢሆን ስለቅማንት ተጨባጭነት ያለውን ጥናታዊ ጽሑፍ የምናገኘው ጆሃን ማርቲን ፍላድ ከተባለ የጀርመን ሚሲዮናዊ ነው። ፍላድ በኢትዮጵያ ከፈላሻዎችና ከቅማንቶች ጋር ለብዙ ዓመታት የኖረ በመሆኑ እሱና የሥራ ባልደረቦቹ በርካታ የሆኑ ፈላሻዎችን በክርስትና ሃይማኖት ያጠመቁ ቢሆንም

ቅማንቶችን ግን ማጥመቅ አልተሳካላቸውም። እንዲያውም ሚሲዮናውያን ጥለውላቸው የሄዱትን መጽሐፍ ምንነቱን ባለመረዳት በማዕከላዊ የቅማንት አገር ከአንድ መቶ ዓመት በኋላ ከተደበቀው ቦታ አገኘሁት።

ቅማንቶች በራሳቸው ቋንቋ የተጻፈ አንድ ምስጢራዊ የጥንቆላ መጽሐፍ እንዳ ላቸው ጐንደር ከተማ የሚኖሩ በሥራዬ ሊረዱኝ ጉጉት ያደረባቸው አንዳንድ አማራዎች ባይነግሩኝ ኖሮ ስለመጽሐፉና በመጽሐፉ ዙሪያ ስለነበረው አጉል ግንዛቤ ጭራሹኑ ተዳፍኖ ይቀር ነበር። በእነሱ አባባል ይህ መጽሐፍ ከተገኘ ስለቅማንት ሃይማኖት ትክክለኛ ገጽታና ስለዓለም ስለአላቸው አመለካከት ማወቅ እንደሚቻል ነበር። እኔም በበኩሌ ቅማንት የሚናገረው የኩሽ ቋንቋ ስለሆነ በምንም ዓይነት ኩሽ የራሱ የሆነ ሥነጽሁፍ ስለሌለው ቅማንትን በራሳቸው ቋንቋ የተጻፈ መጽሐፍ ሊኖራቸው እንደማ ይችል ነግሬአቸው ነበር። እንዲሁም አንድ የኅብረተሰብ የመስክ ጥናት ሊሟላ የሚችለው የኀብረተሰቡን ዕለታዊ ተግባርና ኑሮ በቅርብ በመከታተል፣ በመመልከትና አብሮም በመሳተፍ በአንድ ዓመት ጊዜ ውስጥ በቂ ግንዛቤ ማግኘት እንደሚቻል በመገንዘቤ ስለሚስጥራዊው መጽሐፍ «ፍለጋ» ትኩረት አልሰጠሁትም ነበር።

በመጨረሻም አንዳንድ ቅማንቶችን መጠጥ በመጋበዝና ተደጋጋሚ ጥያቄዎችን በማቅረብ መጽሐፍ ከተደበቀበት ቤትና ቦታ ላይ ደረስኩ። ከዚያም ቅማንቱ ሽፋኑን አንስቶ አንድ አምስት በስምንት አጥቅ (ኢንች) የሆነ የሻገተ መጽሔት አስረከበኝ። ማንበብና መጻፍ የማይችሉት ገበሬዎችና ቀሳውስት ከበውኝ ስለሁኔታው ተገርመው ሲንጫጩ የመጽሐፉን አርእስት ሳነበው «አን አደራ ያሱስ ክርስቶስ ኳደሰው ዋንጋል ሳፋው ሳና ኳድሰው ማርኮስ» የሚል ሆኖ ተገኘ። ትርጉሙ፣ «መጽሐፍ ቅዱስ፣ ቅዱስ ማርቆስ እንደጻፈው» ነው። ይህ መጽሐፍ (ምናልባትም መስሎቹ በቅማንት አካባቢ ተደብቀው ሊሆን ይችላል) የፍላድ ተከታዮችና ጓደኞቹ የሆኑት ሚስዮናውያን ከጀርመንኛ ወደ አገዋዊ ቅማንትኛና የፈላሻ አገው ቋንቋ የተረጐሙት ትንሽ መጽሐፍ ሆኖ ቪየና በሚገኝ የግዕዝን ፊደላት ማተም በሚችል አሳታሚ ድርጅት የታተመ መሆኑን ተረዳሁ።

ፍላድ በቅማንት ሀገር በኖረበት ወቅት ሴቶች በጠር አበባ ጊዜ ማድረግ ስለማይ ግባቸው የተከለከሉ ነውሮች፣ በከፍተኛ ደረጃ ስላሉ ቀሳውስትና በድግና /ደ.ን/ አካባቢ ስለሚካሄደው ክብረ-በዓልና ሥርዓተ-ቅዳሴ ሳይዘግብ አላለፈም። (1866 19)። ይህ ፀሐፊ ፈጽሞ ተጨባጭነት የሌላቸውና ሊታመኑ የማይችሉ አፈ-ታሪኮችን በመጠኑም ቢሆን በከፊል ወደ ማመኑ ደረጃ ተቃርቦ ነበር። ከነዚህም ተረቶች መካከል በቅርብ ዘመዳሞች የግብረ-ሥጋ ግንኙነት እንደሚደረግ አንድ ሰው ወደ ሞት አፋፍ ሲደርስ የተፈጥሮ ሞት ከሚሞት ይልቅ ቄስ ተጠርቶ አንገቱን እንዲቆርጥ ጠዘተ የመሳሰሉት ተቀባይነት የሌላቸው አሉባልታዎች ይገኙበታል። (1866 18) ነገር ግን ሚስዮናዊው ፍላድ ቅማንት ማንኛውንም የሃይማኖት ሥነሥርዓት ሚስጥራዊ በሆነ መንገድ ከነሱ በስተቀር ማንም ሌላ ሰው ሳያውቀውና ሳይሰማው የሚከናወን በመሆኑ ለዚህ መስረተቢስ ለሆነ ሠይጣናዊ አስተያየት ምክንያት ሳይሆን እንዳልቀረ በኋላ መገንዘቡን ያስረዳል። የእሱንም እግር ተከትሎ የመጣው ሄንሪ እስተርን የተባለው ሚሲዮናዊ ቅማንቶች ስለሃይማኖታቸው ምንም ዓይነት መረጃ እነደማይሰጡ ነው የሚያጠናክረው። በተወሰነ ጊዜ ግን ወደ ቋጥኝ ሄደው ሚስጢራዊ አምልኮት እንደሚያካሄዱ ገልጿል።

ሌላው ኢትዮጵያን የጐበኘ ማርቲን ቮን ሐውግሊን የተባለ ጀርመናዊ ነው። እንደ ሐውግሊን አገላለጽ በቅማንትና በአማራው የገዢ መደብ መካከል የማኅበራዊና የፖለቲካ ትስስር እንደነበርና ከቅማንት ልማዳዊ አፈ-ታሪኮች እንደተገነዘበም ጽፏል። በማከልም «ቅማንቶች በታማኝነታቸውና በጀግንነታቸው ምክንያት ንጉሠ ነገሥቱ እጅግ በጣም ብርቅዬ ባለሚሎቻቸውና የቤተሰቦቻቸው ጠባቂ ያደር ጓቸዋል» ይላል። (1868 256)

በቅማንቱና በአማራው የአመራር መደብ ጋር የነበረው የፖለቲካና የወታደራዊ ትብብር የተጠናከረ የቅርብ ግንኙነት በመፍጠሩ የንጉሠ ነገሥቱ ቋሚ ዋና ከተማ የሆነችው ጐንደር በቅማንት መሬት መሐል ላይ በ1630ዎቹ ዓ.ም. እንድትመ ሠረት ማስቻሉን ሐውግሊን ገልጾታል። እንዲያውም አብዛኛው ክርስቲያን አማራ ከሚያስበው በላይ የቅማንት ባለሚሎች በፖለቲካው ውስጥ ምን ደረጃ እንዳላቸው በግልጽ ስለሚያውቁና እንደ አማራውና ትግሬው ባላባቶች የክልል ሥልጣን ፈላጊዎችና የሥልጣን ተቀናቃኝ ባለመሆናቸው የአማራው ነገሥታት

በቅማንቱ ላይ የበለጠ እምነት ጥለውባቸው እንደነበረ ነው:: የአማራውና የቅማንቱ መተባበር ቅማንት ጥንታዊውን አረማዊ አረታዊ ሃይማኖቱን እንደያዘ እንዲቆይ ረድቶታል:: ሌሎች አረታዊ የአገው ሕዝቦች ለብዙ መቶ ዓመታት በተካሄዱ ደም አፋሳሽ በሆኑ ጦርነቶች ቀስ በቀስ በአማራው ሲደመሰሱ ቅማንቶችን ግን ለጊዜው ሃይማኖታ ቸውንና ባህላቸውን እንደያዙ በሰላማዊ መንገድ በፍላጐታቸው ክርስትናን እንዲቀበሉ ተዋቸው::

በ1860ዎቹ ዓ.ም ወደ አፄ ቴዎድሮስ የተላከው የእንግሊዝ ቡድን አባል የነበረው ሆርሙዝድ ራሳም ደግሞ ሲገልጽ «ከአፄ ቴዎድሮስ በስተቀር በማንኛውም ጊዜ ቢሆን እንደ የሃበሻ ንጉሥ እንደ ቅማንቶች ያለ ታማኝ፣ ባለሟሎች አግኝቶ አያውቅም» ይላል:: (1865፣1፣209):: ቅዱስ ቦታዎች ናቸው ብለው በሚያምኑባቸው ድግናዎች (ደኖች) ስለሚደረገው ሥርዓተ-ቅዳሴ ሲያብራራ «ሃይማኖታቸው ልክ በሶሪያ እንደሚገኙት አንሳሪስ ሕዝብ እጅግ በጣም ሚስጥራዊ ነው፣ በክርስቲያኑም ሆነ በእስልምናው ዓለም ያልታወቀ ሥርዓተ-ቅዳሴና ሥነሥርዓት ያካሂዳሉ» በማለት ዘግቧል:: (1869፣1፣ 209)::

ለሁለት መቶ ዓመታት ያህል ስለቅማንት በአውሮጳውያን የተሰጡትን ተባራሪ የሆኑ አስተያየቶችን በማሰባሰብና የራሱን የመስክ ጥናት በማካሄድ ፍሬድሪክ ሲሙንስ የተባለ አሜሪካዊ የጂኦግራፊ ምሁር ነበር ሠፋ ያለ ጥናት ያካሄደው:: እ.ኤ.አ ከ1953-1954 ባለው ጊዜ በቤጌምድርና ሰሜን ጠቅላይ ግዛት ስለሚገኙት ቅማንቶች ያደረገው ጥናት ያለንን እውቀት አዳብሯል:: ወደፊት እንደሚገለፀው «ሰሜናዊ ምዕራብ ኢትዮጵያ (በ1960)» የሚለው አስደሳች ጥናታዊ መጽሐፍ ነበር ስለቅማንት የመስክ ጥናቴ መሠረታዊ መመሪያ የሆነኝ::

ብዙውን ጊዜ አንድ የሥነ-ሕዝብ ተመራማሪ የመስክ ጥናት ለምን እንደሚ ያካሂድ ዓላማውን ጥናቱ ለሚካሄድበት ኅብረተሰብ አስረድቶ ተቀባይነት ለማግኘት እንደሚቸገር ግልጽ ነው:: በተለይም ለምዕራ ባዊው ዓለም ባህል ተጋልጠው ለማያውቁት ለቅማንት ገበሬዎች እውነትነቱ የማይታበል ነው:: ማንበብና መጻፍ ስለማይችሉ ፀጉረ-ልውጦች የሚያደርጉትንና በተለይ

አጥኚው በጽሑፍ ለማስፈር የሚያደርገውን ጥረት ሁሉ በጥርጣሬ ይመለከቱታል፡፡

በተማረው ክፍል በእጅ የተጻፉ ታሪካዊ ሥነ-ጽሑፎች በቤተክርስቲያን ውስጥ ይቀመጡ ስለነበር እኒም ስለቅማንትና ጉረቤት ስለሆኑዋቸው አማራና ፈላሻ ታሪክና ባህል መጽሐፍ እንደምጽፍ አስረዳሁ፡፡ በጉዳዩ ላይ ላለመተባበር ሲያቅማሙ ሲሙንስ የጻፈውን መጽሐፍ አውጥቼ ሌሎች አውሮጳውያን ከጸፉት አንዱ መሆኑን ሳሳያቸውና የቅማንት፣ የፈላሻና የአማራ ሰዎች ፎቶግራፎች መኖራቸውን፣ እንዲያውም አንዳንዶቹ በአጋጣሚ የራሳቸውንና የሚያውቋቸውን ሰዎች ፎቶግራፎች በተመለከቱ ጊዜ በተመሳሳይ ሁኔታ አስቀድሞም ይኸው ዓይነት ጥናት መካሄዱን በመገንዘባቸውና በሰዎችም ላይ ምንም ዓይነት እንከን አለማጋጠሙን በማመዛዘን ሊረጋጉና ሊተባበሩኝ ቻሉ፡፡

በሲሙንስ አገላለጽ «እምነታቸውና ሥነ-ሥርዓታቸው ምስጢራዊ ስለሆነው» (1960:30) ስለቅማንት ማንነት ከማወቅ ችንና የዕለት ተዕለት ተግባራቸውን እያከናወኑ ኑሮአቸውን እንዴት እንደሚመሩ ከማየታችን በፊት ስለቅማንትና ጥንታዊ ቅድመ-ቅድመ-አያት ስለሆነው የአገው ሕዝብ ታሪካዊ አመጣጥ እንመለከታለን፡፡

# ምዕራፍ ሁለት

## የአገው ባህል ታሪክ ፈጣን እድገት

የአገው ቅርንጫፍ ስለሆነው የቅማንት ሕዝብ ታሪክ ለማወቅ እንዲረዳን የአገው ሕዝቦች የባህል ታሪክ እድገት እንደመን ደርደሪያ እንደሚከተለው በአጭሩ ቀርቦአል:: በመሠረቱ ስላለፈው ጥንታዊ የኢትዮጵያ ታሪክ ብዙም አልተጻፈም:: ስለሀገሪቱ ቅድመ-ታሪክና ታሪክ አንዳንድ በጣት ሊቆጠሩ የሚችሉ አጠቃላይ ሥራዎች ቢኖሩም አገው በማዕከላዊነት ስለነበረው ታሪካዊ ድርሻ እንዳቸውም ከሞላ ጐደል እንኳን አይገልጹም::

## ቅድመ-ታሪክ

በ5,000 ዓመተ ዓለም እና ምናልባትም ከዚያ በፊት ቡሽማኖይድና ኮኬዥያን የተባሉት የሰው ዘሮች በደጋማው ኢትዮጵያና በአካባቢው በአዳኝነትና በፍራፍሬ ለቃሚነት ይኖሩ ነበር:: የኮኪዥያን አዳኞችና ፍራፍሬ ለቃሚዎች የነበሩት ያለጥርጥር ቅማንትን ጨምሮ በአሁኑ ወቅት በኢትዮጵያ ያሉት የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪ ሕዝቦች ጥንታዊ ዘረማንዘራቸው እንደነበሩ እንረዳለን::

የዕፅዋት ጥናቶች እንደሚያመለክቱት ምንም እንኳን ዕፅዋትን በማለማመድ ጥንታዊት ኢትዮጵያ ሙሉ በሙሉ ብቸኛዋ አገር ባትሆንም ሰብሎችን በማለማመድና በማሠራጨት ከፍተኛ ድርሻ ነበራት:: በሰሜንና በማዕከላዊ ኢትዮጵያ አሁን ያለውን የአገው ሕዝብ አሠፋፈር ስናጠና ሰብልን የማለማመድንና ማሠራጨትን ሥራ ሲያከ ናውኑ የነበሩት ቡሽማኖይድ ሳይሆኑ የጥንት የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪ ሕዝቦች መሆናቸውን እንገነዘባለን:: ጥንታዊ አገው ከሌላ አገር በስርጭት የደረሰውን ስንዴና ገብስ የመሳሰሉትን የተለያዩ ሰብሎችን ያመርት እንደነበረና እነሱም በአካባቢያቸው የሚገኙትን መበላት የሚችሉ ሌሎች ሰብሎችን በማለማመድና አገልግሎት ላይ በማዋል የታወቁ ነበሩ:: ለመጥቀስ ያህል ጤፍና ዳጉሣ፣ እንዲሁም የቅባት እህል የሆኑትን ኑግና

ተልባን አለማምደው ያሰራጩት አገዎች ናቸው:: የአዝእርትና የአትክልት ማልማት ዘዴ ከክርስቶስ ልደት ከ3,000 ዓመት በፊት በጥንታዊ አገዎች ዘንድ የታወቀ ሲሆን እንስሳትን ማለማመድ ደግሞ ከክርስቶስ ልደት ከ2000 ዓመት በፊት ከኑቢያኖች እንደተማሩ ታውቋል::

ዕፅዋትን የማለማመዱ ዘዴ ለኢትዮጵያ ከኬኘር ያኖች በቡሽማኖይዶች ላይ የባህል የበላይነትን ሳያቀዳጃቸው አልቀረም:: በመሆ ኑም ሕዝባቸውም እየበዛ በመሄዱ አካባቢያ ቸውን በመቆጣጠር ጥቅም ላይ በማዋል፣ ሕዝቡን አደራጅተው ለጦርነት ለማዘጋጀት ምቹ ሁኔታ ስለተፈጠረላቸው የቡሽማ ኖይድ ዝርያዎችን በአብዛኛው ከአካባቢያቸው እንዲሰደዱ ሲያደርጉ አንዳንዶቹ ደግሞ በተለያየ መልክ በባሕል ለውጥና በመዳቀል ተውጠው እንዲቀሩ ሆኖአል::

ከ1000 ዓመተ ዓለም ቀደም ብሎ የደቡብ አረቢያ ሕዝቦች ባሕላቸውን ይዘው ወደ ሰሜናዊ የአገው አገር አካባቢ ከመምጣታቸው በፊት የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪዎች መላ ኢትዮጵያን ተቆጣጥረው እንደ ነበርና እንዲያውም ወደ ደቡብ በመስ ፋፋት ድንበርተኛ ወደሆኑት አሁን ኬንያ፣ ኡጋንዳና ታንዛኒያ እየተባሉ ወደሚጠሩት አገሮች ሳይቀር መሠራጨ ታቸው የታወቀ ነው::

## ኢትዮጵያዊ ሥልጣኔ

ከክርስቶስ ልደት በፊት ከ2000 ዓመተ ዓለም መጨረሻ ላይ አነስተኛ ዝናብ በነበረባት የመን በመስኖ የእርሻ ኢኮኖሚ ላይ የተመሠረተ ሥልጣኔ ነበር:: ከ1000 ዓመተ ዓለም በኋላ በደቡብ አረቢያ ከሚገኙ አገሮች እየተነሱ አንዳንድ ጐሣዎች ከተከዜ ወንዝ በስተሰሜን የሚገኘውን ደጋማውን የኢትዮጵያ ክፍል ቅኝ ግዛት ማድረግ ጀመሩ:: ይህም ሂደት ለ1000 ዓመት ያህል ሳይቋረጥ አልቀረም:: በዚያን ጊዜ ከደቡብ አረቢያ የመጡ ት ሕዝቦች የተገናኙት አስቀድሞ ሠፋሪና ነዋሪ ከሆኑት የአገው ጥንታዊ ቅድመ-ቅድመ-አያቶች ጋር ነበር::

የደቡብ አረቢያ ባህልና የጥንታዊው አገው ባሕል በመቀላቀላቸው ሦስተኛ ባህል ሊፈጠር ችሏል:: ነገር ግን ጠቅላላ ውሕደት ስላልተከሰተ ነባሩ ባህልም ሆነ ከደቡብ አረቢያ የመጣው

እንዲ ሌላውን ጨርሶ ሳይደመስስ የየራሳቸውን የባህል ትውፊት በመያዝ ቆዩ:: የማኅበራዊና የባህል እድገት በዚህ ዓይነት መዳቀል ምክንያት አንድ ደረጃ ከፍ በማለቱ «ኢትዮጵያዊ ሥልጣኔ» እያልን የምንጠራው አቆጥቁጦ ወደ ደቡብ በመዛመቱ ኢትዮጵያ የጥንታዊ ሥልጣኔ በር ከፋችና ማዕከል ሆነች::

የደቡብ አረቢያ ሕዝቦች ለኢትዮ ጵያዊው ሥልጣኔ ብዙ አስተዋፅኦ አድርገዋል:: ለመጥቀስ ያህል:- የጥሬ ካብ ሥራ፣ የሐውልት ሥራ፣ ከእርከን ጋር የተያያዘ የመስኖ ሥራና ምናልባትም ማረሻና ቀንበርን ማስተዋወቅ የመሳሰሉት ከብዙዎቹ ጥቂቶቹ ናቸው:: በተጨማሪም ውስብስብ የሆኑ የማኅበራዊ አደረጃጀት ስልት በተለይም በመጀመሪያው ምዕራፍ ላይ የተገለጸው ባለሁለት መደብ ማኅበራዊ ተቋም፣ ማለትም በአንድ በኩል የነቃውን ክፍል ያቀፈው «ባለ ታላቅ ባህል» እና በሌላ በኩል ደግሞ አርሶ አደሩንና ሌሎች ዝቅተኛ የሕብረተሰብ ክፍሎችን ያጠቃለለው «ባለ ትንሽ ባህል» እየተባለ የሚታወቀውን አደረጃጀት የደቡብ አረቢያ ሕዝቦች ይዘውት የመጡት ሥርዓት ነው:: ከሁሉም በላይ ልቆ የሚታየው አስተዋፅኦ ደግሞ የጽሑፍ ፊደላትን ማስተዋወቃቸው ነው:: ምንም እንኳን የደቡብ አረቢያ ሕዝቦች ቁጥራቸው አነስተኛ ቢሆንም ቋንቋቸው ወይም ደግሞ የእነሱን ቋንቋ የተካው ግዕዝ ባለሥነጽሑፍ ቋንቋ ስለነበሩ ከሌሎች ቋንቋዎች ሁሉ የበላይነትን ሊቀዳጅ ችሏል::

ጥንታዊ የአገው አባቶችም ቢሆኑ ለኢትዮጵያ ሥልጣኔ ብዙ አስተዋፅኦ አድርገዋል:: አብዛኛው የሕዝብ ክፍል ስለነበሩ አሁን የምናየው ኢትዮጵያዊ የእነሱን ልዩ የሰውነት መልክና ቅርጽ እንዲይዝ ሆኖአል:: በተጨማሪም በግብርናው ሥልጣኔ በኩል ጥንታዊ አገዎች የአደረጉት አስተዋፅኦ በቀላሉ የሚገመት አይደለም:: በደቡብ አረቢያ ቀደም ብሎ የሚታወቁትን ስንዴና ገብስ እንዲስፋፉ ከማድረጋቸውም በላይ ሌሎች ለምግብነት የሚያገለግሉ መሠረታዊ የሆኑ አገር በቀል ሰብሎችን በማለማመድ እንዲሠራጩ ያደረጉት አገዎች ናቸው::

ቀጥሎ በነበሩት መቶ ዓመታት ብዙ የሥልጣኔ ማዕከሎች ተመሥርተው ነበር:: ከክርስቶስ ልደት ወዲህ በጣም ሥልጣኔ ተስፋፍቶ የነበረው ግን የሃይማኖት ሐውልቶች በብዛት ተሠርተው በነበሩበት በአክሱም ከተማ ነበር:: የአራት ሃይማኖት እምነት

ከደቡብ አረቢያ አስቀድሞ ወደ ኢትዮጵያ ተሠራጭቶ የነበረ ቢሆንም የኢትዮጵያ አክሱማዊ መንግሥት ገዥ በነበረው በንጉሥ ኢዛና ዘመነ መንግሥት በአራተኛው መቶ ክፍለ ዘመን ክርስትና ወደ ኢትዮጵያ በመግባቱ የክርስትና ሃይማኖት በአክሱም ከተማ ነዋሪዎች ከተጠናከረ በኋላ በስፋት በገጠሬቱ ኢትዮጵያ ገበሬዎች ስር ሊሰድ ችሏል።

ከጊዜ በኋላ ግን ኢትዮጵያ በደቡብ አረቢያ ይዛው የነበረችውን ግዛቷን በፋርስ መንግሥት በመነጠቋ ሥልጣኗዋ እየተዳከመ መጣ። የእስልምና ሃይማኖት እየተስፋፋ በመምጣቱ ወደ ሜድትራኒያን፣ አረቢያና ምሥራቅ አፍሪካ ወደእሉ የንግድ ማዕከሉች የሚደረገውን የኢትዮጵያውያን የንግድ እንቅስቃሴ ተገታ። ከሌላው ዓለም ጋር የሚያገናኛት የቀራት አንድ በር ደግሞ በ8ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪ የሆኑት የቤጃ ጐሣዎች ተነሥተው አክሱምን በመውረር ከሌሎች የኑቢያ ክርስቲያን መንግሥታት ጋር የነበረውን መንገድ በመስበር በመዝጋታቸው ግንኙነት ተቋረጠ። የመጨረሻው ወድቀት ደግሞ አዲሱን ኢትዮጵያዊ ባህል ያልወደዱት አንዳንድ የአገው ሕዝቦች በአመፅ መነሣሣት ነበር። (ይህንን በሚቀጥለው ንዑስ ክፍል እናየዋለን) ። ኤድዋርድ ጊቦን በኢትዮጵያ ስለተከሰተው ጠቅላላ ሁኔታ ሲገልጽ፣ «በሃይማኖት ጠላቶቻቸው ዙሪያውን ተከበው ዓለምን እረስተው፣ ዓለምም ራሷ እነሱን እረስታቸው ኢትዮጵያ ውያን ለአንድ ሺ ዓመት ያህል አንቀላፉ» በማለት ይደመድመዋል።

## ኢትዮጵያዊ ሥልጣኔ ወደ ደቡብ ስለመስፋፋቱ

ኢትዮጵያዊው ሥልጣኔ ተመናምኖ ተዳከመ እንጂ ጨርሶ አልወደመም ነበር። በቤጃዎችና በእስልምና ኃይሎች የተከበበው ተራፊው የኢትዮጵያ ሥልጣኔ ኃይሉን በመካከለኛው የኢትዮጵያ ደጋማ ደልዳላ አካባቢ እንደገና ማጠናከር ጀመረ። እ.ኢ.አ. በ900 ዓ.ም. አካባቢ የሰሜኑ ሕዝብ በከፊል ተከዜን ተሻግሮ አገዎችን እየገፋ መስፈር ቀጠለ። ቀጥሎም ለረዥም ዘመናት የአገውና የሴም ቋንቋ ተናጋሪዎች በአንድ ላይ በመኖራቸው ምክንያት በመካከላቸው መዳቀል ተከተለ። ከሁለቱ ሕዝቦች የኢትዮጵያዊ ሥልጣኔ መሥራች ስደተኞች በወታደር ኃይል በደብልጥ የተጠ

ናቸሩ ስለነበሩ ተዕለኛ ማድረግ በመቻላቸው የሁለቱ ሕዝቦች መቀላቀል በመፋጠኑ ውሕደት በሂደት በመከሰቱ «የመጀመሪያው አማራ» (ፕሮቶ-አማራ) ብቅ አለ:: ተከዜን ሳይሻገሩ እዚያው የቀሩት ኢትዮጵያውያን ደግሞ የአሁኖቹ የትግሬ ሕዝብ ቅድመ-ቅድመ-አያቶች ነበሩ::

የመጀመሪያው አማራ «ባለትልቅ ባህል»ና «ባለትንሽ ባህል» ተብለው በሚታወቁት ሁለት መደቦች የተከፈለ ነበር:: ኃይሉን በከፍተኛ ፍጥነት እያጠናከረ ኋላቀር የሆኑትን አገዎች በቁጥጥሩ ማድረጉን ቀጠለ:: ከተከዜ በስተደቡብ የነበሩት አገዎች ከጥንታዊው አማራ ሕብረተሰብ ጋር በመቀላ ቀላቸው የማኅበራዊና ባህላዊ ለውጥ በማስከተሉ ቀጣዩ ክስተት የሁለት ሕዝቦች ውሕደት ሆነ:: ውሕደቱም የአማራው አካል የሆነው ሦስተኛው ዓይነት ባህል እንዲፈጠር ረዳ:: ምንም እንኳን ብዙት ባለው የአማራ ሕዝብ ቢከበቡም ይህ የባህል ውሕደት ሲካሄድ ቅማንቶችና አንዳንድ ሌሎች አገዎች ማንነታቸውንና ባህላቸውን ጠብቀው የኖሩ አልጠፉም::

የባህል ልውውጡ በእንኳ-በእንኳ ቢሆንም የጥንታዊ አማራ ባህል የበላይነቱን መያዝ ቻለ:: በዚህም ምክንያት ቋንቋው የአገው ቅሪት ሳይለየው ሴማዊ ሆኖ ሃይማኖቱ ደግሞ በጊዜው የአረማዊ-አሪታዊ እምነቶችን ያካተተ የክርስትና ሃይማኖት ነበር:: በግብርናው ረገድ አማራው በአብዛኛው የሚያመርታቸው ሰብሎች በአገዎች የተላመ ዱትን የእህልና የአታክልት ዓይነት ሆነ:: የመጀመሪያው የአማራ ባህል ከጥንታዊው አገውና ከደቡብ አረቢያ ከመጡት ተስፋፊዎች ባህል ጋር አስቀድሞ የተዳቀለ ሲሆን ዘግየት ብሎም በዘመናት ሂደት በተጠናከረ ሁኔታ ከአገዎች ጋር በሁለተኛ ደረጃ የባህል ውሕደቶች እንደተካሄዱ እንገነዘባለን::

አገዎች ከጥንታዊው አማራ የተማሩት የቴክኖሎጂና የአደረጃጀት ስልት አካባቢውን መቆጣጠር ስላስቻላቸው ቀደም ብሎ ቅድመ-አያቶቻቸው ሳይጠቀሙበት የቀረውን የመሬት ሀብት መጠቀም አስቻላቸው:: ባለማረሻ ሞፈርና ቀንበር ሌሎች የብረት መሣሪያዎ ችንና የእርሻ ዘዴዎችን ተግባራዊ በማድረግ ሠፋፊ መሬቶችን ማረስ ጀመሩ:: የተሻለ ጥልቅ እርሻ በማረስ፣ ረግረጋማ ቦታዎችን በማድረቅና የመስኖ ሥራንም በመጠቀም

ከረምት ከበጋ ማምረት በመቻላቸው ምርት ተትረፈረፈ። የቴክኖሎጂ ለውጥና የተፋፋመ የኢኮኖሚ ስድገት የሕዝብ ብዛትን አስከተለ። ይህም በተቃራኒው ብዙ ደኖች እየተጨፈጨፉ ወደ እርሻ መሬት በመለወጣቸው የደጋማይቱ ኢትዮጵያ የደን ሃብት ተመና መነ። ደኖች በመጨፍጨፋቸውና ረግረጋማ ቦታዎች ስለደረቁ በመጠኑም ቢሆን ኑሮአቸውን ለመደጎም ይታደኑ የነበሩት የዱር እንስሳት አብረው ጠፉ። የአማራው ቴክኖሎጂ ባስከተለው የአካባቢው ለውጥ ምክንያት ወደ ድሮው ዓይነት ኑሮአቸው አገዎች መመለስ ስላልቻሉ ቀስ በቀስ ባህላቸው እየተለወጠና እየተዋጠ ከአዳኝነትና ከጓሳቀር የጓሮ አታክልት አልሚነት ወደ ገጠሬ ገበሬነት ተሸጋገሩ።

## የባህል ማንኙነት
## በአገው ሕዝብ ላይ ያስከተለው ስሜት

የአንድ አገር ተወላጅ ነባር ሕዝብ አንድ ሌላ ቡድን በኃይል ተፅዕኖ ሲያደርግበት የሚሰጠው ምላሽ ይኖራል። አንዳንድ ጊዜ በዝምታ ሁኔታዎችን ተቀብሎ ወደ አንድ አካባቢ ራሱን ያገላል፡ ሌላው ደግሞ የመጣውን ላለመቀበል ራሱን አደራጅቶ እንደገና ተጠናክሮ በመታገል ከተፅዕኖው ነፃ ሆኖ ሥልጣን ለመያዝ ይፍጨረጨራል። አማራው ተከዜን ተሻግሮ ወደ አገው አገር ማልቀ በመግባቱ ባህላቸው የተለወጠውም ሆነ ያልተለወጠው አገዎች የተቃውሞ እንቅስቃ ሴዎች ማድረጋቸው አልቀረም። ይህ ዓይነቱ እንቅስቃሴ ነበር ከተከዜ በስተሰሜን የነበረውን ኢትዮጵያዊ ሥልጣኔ ለመጨረሻ ውድቀት የዳረገው። በአፈ-ታሪክ የታወቀችው ንግሥት ዮዲት (ጉዲት) የተባለችው ፈላሻ አገው የጦር መሪያ በማንሳት ከአማራውና ከትግሬው ኃይል ጋር ከዘጠነኛው እስከ አስረ እንደኛው ምዕተ ዓመት በተደረጉት የትጥቅ ትግሎች ከተካፈሉት የአገው የጦር መሪዎች አንዷ ሆና በምሳሌነት ትጠቀሳለች።

አብዛኛውን የኢትዮጵያ ክፍል በመቆጣጠር አገዎች መቼ ሥልጣን እንደያዙ የታሪክ ማስረጃዎች በግልጽ ባያስረዱም የላስታ አገዎች የዛጉዌን ስርዎ-መንግሥት አብዛኛውን ጥንታዊት ኢትዮጵያን እ.ኤ.አ ከ1137 እስከ 1270 ዓ.ም ድረስ መግዛታቸው የተረጋገጠ ነው። በዚያ ዘመን ኢትዮጵያ በደንብ የተደራጀ መንግሥት ያላትና ግዛቷ ሰሜንንና ማዕከላዊ ደጋማውን

የኢትዮጵያ ክፍል ያካተተ ነበር። አንዳንድ ጽሑፎችና አፈ-ታሪኮች አገዎች ከዚህ ቀደም ብሎ ሥልጣን ይዘው እንደነበር ያስረዳሉ። ይህም በአገው እንቅስቃሴ ጊዜ የአማራውና የትግሬው ኃይል ቀስ በቀስ እየተሸረሸረ መጥቶ በመጨረሻ መገርሰሱን የሚያስገነዝብ ነው።

አገው ሥልጣኑን በጨበጠበት ወቅት የትግሬውና የአማራው ሥልጣኔ ወደ «ጨለማ ዘመን» ገባ። ብዙም ባይታወቅ የኢኮኖሚው ተቋም ተንኮታኩተ፣ በከተሞች ተቋቁመው የነበሩ ታላላቅ ገበያዎች ፈራርሰው ግብይት በየመንደሩና በየሜዳው ሆነ፣ ከተሞችም የአውሬ መፈንጫ ሆኑ። የአማራውና የትግሬው «ታላቁ ባሕል» ተብሎ የሚታወ ቀውም ሆነ ማቆጥቆጥ የጀመረው ቴክኖሎጂ ተሽመድምዶ ወደ ገጠሬነት ተለወጠ። በመሆኑም የውስጥና የውጭ ግንኙነቶች ተቋርጠው ጉስቁንነት ተስፋፋ። በዚያን ዘመን ነበር ኢትዮጵያዊው ሥልጣኔ በአብዛኛው ጭራሽ የጠፋው ወይም የፈራረሰው።

## ባላባታዊ መንግሥት በኢትዮጵያ ስለማቆጥቆጡ

እ.ኤ.አ. በ1270 ዓ.ም አካባቢ አማራው አመፅ አስነስቶ የመጨረሻውን የዛጉዌ ስርዎ-መንግሥት ንጉሥ በመገልበጥ የመካከለኛውን ክፍለ-ዘመን የኢትዮጵያ ሥልጣነ-መንግሥት በእጁ አስገባ። ይህ የተሳካ እንቅስቃሴ ሥልጣን ወደ ጥንታዊ የኢትዮጵያ ባህላዊ መሪዎች እንዲመለስ በማድረጉ የመጀመሪያው የማዕከላዊ ዘመን የኢትዮጵያ ባላባታዊ አገዛዝ መንግሥት ተመሠረተ። ይህ ባላባታዊ አገዛዝ «በጨለማው ዘመን» አቆጥቁጦ በመካከለኛው ዘመን ደግሞ በሰፊው ተንሠራፍቶ አዲሲቱ ኢትዮጵያ እስከ ተመሰረተችበት እስከ 1890ዎቹ ዓ.ም. ድረስ ቆየ።

መሠረቱን በከተማ ያደረገ ንጉሣዊ አገዛዝ በተረጋጋ መልክ አገዛዙ እንዲቀጥል ለማድረግ የተሻሻለ ዘመናዊ አስተዳደር፣ የመገናኛ ተቋምና የወታደራዊ ቴክኖሎጂ ዕድገት እንደማያስፈልገው እሙን ነው። ይህን ዓይነት መሻሻል ማምጣት ግን በጠላቶቿ ለተከበበችው እንደ ኢትዮጵያ ላለችው ድሃ አገር በጣም አስቸጋሪ ነበር። ስለዚህ የአገሪቱን አንድነት ለመጠበቅ

ሲባል ንጉሣዊዉ ዙፋን ከአንዱ ቦታ ወደሌላው ቦታ መዘዋወር የሚችል ወታደራዊ ሠፈር (ካምፕ) እንዲሆን ግድ ሆነ። በአውሮጳ የነበረውን ባላባታዊ ሥርዓት የተመለከትን እንደሆን ባላባታዊ ግዛቶች በመንግሥት መልክ ተደራጅተው ማዕከላዊ መንግሥት ዕቃዎችን ማከፋፈልና ልዩ ልዩ አገልግሎቶች ይሰጣቸው ነበር። ቤተክርስቲያንና መንግሥት አንዱ ሌላውን እየረዳ በፖለቲካውና በሃይማኖታዊ መሪዎች መካከል ትብብር እንደነበረም እንረዳለን።

አገው በአማራው ሥልጣን ላይ በተነሳበት ወቅት የአማራውን ባህል አልተወውም ነበር። ክርስትና ክብር ያለውና የሥልጣኑ ምልክት በመሆኑ እየተስፋፋ በመሄዱ የውሕደቱ ሂደት እያዘገመ ቀጠለ። ከዚህም በስተቀር አገውና አማራ የሚያመልኩት የክርስትና ሃይማኖት የጥንታዊውን አረማዊና-አሪታዊ አንዳንድ እምነቶችን ያካተተ ስለነበር ክርስትና በፍጥነት እንዲስፋፋ ረድቷል። አማራው ሥልጣን ከያዘ በኋላም የሁለቱ ሕዝቦች የመቀላቀል ሂደት በፍጥነት ቀጥሎ የቀሩት አገዎች ደግሞ እንደገና በአማራው የገዥ መደብ ሥር ወድቀው በገጠሩ የግብርና ኑሮአቸውን ተያያዙት። በአንዳንድ አካባቢዎች የባህል ለውጡ በጣም ቀስ ያለ ነበር። እንዲያውም እንደቅማንት ያሉ አንዳንድ የአገው ቅርንጫፎች ብዛት ባለው የአማራ ሕዝብ የተከበቡ ቢሆንም ጭራሹኑ ሳይለወጡ ቆዩ። ጥቂት አገዎች ከአማራው ጋር ተቻችለው በመኖር ውሕደቱን በመግታት ልዩ የሆነውን የራሳቸውን «ትንሽ ባህል» ይዘው ሲቆዩ ከቅማንቶች በስተቀር ሌሎች አገዎች በመሣሪያ ሳይቀር አማራውን በመቃወም ለአራት መቶ ዓመታት ያህል ሲታገሉ ቆይተዋል።

መካከለኛው ዘመን እየገፋ ሲሄድ የአማራው ሕዝብ ብዛት እየተበራከተ በመምጣቱ መሪነቱን ጨበጠ። የአገው ሕዝብ በብዛት ብልጫ ስለነበረው በመጀመሪያ የባህል መቀላቀሉን ሂደት ደግፎት ነበር። ነገር ግን የሕዝብ ብዛቱ እየቀነሰ በመምጣቱ ተፅዕኖ የማድረግ ኃይሉ ስለተዳከመ፣ የባህል ለውጡ ቀስ በቀስ የአማራና የአገው ባህል መቀላቀል በእንካ-በእንካ መሆኑ ቀርቶ የአገዎችን በአማራ ጨርሶ መዋጥን (ውህደትን) አስከተለ። የባህልና የሃይማኖት ጨርሶ መዋጥ ሁኔታ በ15ኛው ክፍለ ዘመን የተከሰተ ሲሆን ሂደቱን «አማራ መሆን» (አምሃራይዜሽን) እንለዋለን።

ደ.ጋው ኢትዮጵያ እ.ኤ.አ በ1527ዓ.ም በእስላሞችና ቀጥሎ ደግሞ የምሥራቅ የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪ አንዱ በሆነው የኦሮሞ ሕዝብ ተጠቅቶ ነበር:: በተጨማሪም በዚያን ጊዜ አማራው ባህላቸው ካልተለወጠው ጎራ ከሚገኙት አገዎች ጋር ፋታ በማይሰጥ ጦርነት ተጠምዶ ቆየ:: በ13ኛው መቶ ክፍለ ዘመን አማራው ሥልጣኑን እንደገና አደላድሎ ከያዘ በኋላ ኢትዮጵያ ከምዕራቡ ዓለም ጋር ግንኙነት ተጀምሮ ነበር:: በልዑል ሄነሪ ዘ-ናቪጌተር ዘመን የመርከበኝነት ቴክኖሎጅና ከመስፋፋቱም በስተቀር ለክርስቲያን መስዋዕ ትነት ለመክፈል የፖርቱጊዞች ወኔ በመነሳሳቱ ከኢትዮጵያ ጋር ግንኙነት እንዲጀመርና ተጠናክሮም እንዲቀጥል በር ተከፈተ:: እ.ኤ.አ በ1540 ዓ.ም. ወታደራዊ እርዳታ ከፖርቱጋል ተልኮ በኢትዮጵያ ከፍተኛ ጥፋት ያደረሰው የሙስሊሞች ወረራ (የግራኝ መሐመድ ወረራ) እንዲገታ ረድቷል:: ፖርቱጊዞች ጠብመንጃን ስላስተዋወቁዋቸው በየጊዜው እየተነሱ የሚያስቸግሩትን አገዎች አማራው እንዲያንበረክክላቸው ከማስቻሉም በላይ ድንበራቸውን ከእስላሞች ለመከላከል የሚያበቃቸው አስተማማኝ ሁኔታ ተፈጠረላቸው:: ቀጥሎም በአማራው ክልል የነበሩት የኦሮሞ ሕዝብ በአማራው የባላባታዊ አገዛዝ ሥር ወድቀው አብዛኛው የአማራን ባህል እንዲከተሉ ተደረገ:: በ1630ዎቹ ዓ.ም የፖርቱጊዝ ቀሳውስት በሮማው ቤተክርስ ቲያንና መሠረቱ በአሌግዛንድሪያ በሆነው የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተክርስቲያን ሃይማኖት ተከታዮች መካከል ብጥብጥ በመነሣቱ የኢትዮጵያ መሪዎች ጀስዊቶችን በማገለል የፖርቱጊዞችን ተፅዕኖ ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ እንዲቆም አደረጉ::

## አዲሲቱ ኢትዮጵያ

እ.ኤ.አ. በ1630ዎቹ ዓ.ም ቋሚ ርዕስ ከተማ የሆነችው ጎንደር በቅማንት መሬት ላይ ተመሠረተች:: ፖርቱጊዞች ከመባረራቸው በፊት ለጐንደር ግንባታ የአርኪቴክትና የምሕንድስና ሥራ አስተዋፅዖ አድርገዋል:: ከእክሱም ወዲህ ጎንደር የመጀመሪያ ቋሚ መዲና ሆና ልትመሠረት የቻለችው አማራው በአጠቃላይ የፓለቲካውን የበላይነት በመያዙና ቅማንቶችም ይህን ያህል ተቃውሞ ባለማሳየታቸው ነበር:: በመሆኑም ጎንደር እስከ እ.ኤ.አ 1880ዎቹ ዓ.ም ድረስ የኢትዮጵያ ዋና ርዕስ ከተማ ሆና ቆየች::

በ1870ዎቹና በ1880ዎቹ ዓ.ም ግብጽና የሱዳን ማን ዲስት (ደርቢሾች) ኢትዮጵያን ለመውረር በሞከሩ ጊዜ አፄ ዮሐንስ አራተኛ ሀገሪቱ በቅኝ አገዛዝ ሥር እንዳትወድቅ ተከላከለዋል። ቀጥሎም እ.አ.አ ከ1889 እስከ 1913ዓ.ም ኢትዮጵያን የገዙት ዳግማዊ አፄ ምኒሊክ አውሮጳውያን ሀገሪቱ ውስጥ ገብተው ለመያዝ የሚያደርጉትን ሙከራ ጣሊያኖችን አድዋ ላይ በማያዳግም ሁኔታ ድል በመምታት የነበራቸውን የቅኝ አገዛዝ ምኞት አንኮታኩቱት። ምኒልክ ግዛታቸውን ወደ ደቡብ ኢትዮጵያ በማስፋፋት አዲስ አበባን የመናገሻ ዋና ከተማ አድርገው በመቆርቆር የምዕራባውያን ዘመናዊ የከተማ ኢንዱስትሪና ቴክኖሎጂ በአገሪቱ እንዲታወቅ አደረጉ። በምኒልክ ዘመነ መንግሥት ነበር ኢትዮጵያ ተስፋፍታና አድጋ ዘመናዊ የሆነ የኢትዮጵያ መንግሥት የተቋቋመው።

በአሁኑ ወቅት ባሉት በቀዳማዊ አፄ ኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥትም ለውጥ በፍጥነት እየተራመደ ነው። ምንም እንኳን እ.ኤ.አ ከ1936 እስከ 1941 ዓ.ም በንጉሠ ነገሥቱ አገዛዝ ዘመን ኢትዮጵያ ዘመናዊ መሣሪያ በታጠቀው በጣሊያን ወታደራዊ ኃይል በቅኝ አገዛዝ ሥር ብትቆይም ዛሬ አገሪቱ በዘመናዊ አስተዳደር መልክ ተደራጅታ የሀገሪቱ የኢንዱስትሪና የሥልጣኔ መሠረት ይሆናል ተብሎ ሠፊ የትምህርት ፕሮግራም ስለተዘረጋ ቀስ በቀስ ኢትዮጵያን ወደ ኃያል ዘመናዊ ሀገር ያሸጋግራታል ተብሎ ይታመናል።

# ምዕራፍ ሦስት

## የቅማንት ኅብረተሰብና አሠፋፈሩ

ጥናቱ የተካሄደባቸው የቅማንት ኅብረተሰቦች ግንኙነታቸው ከእርስ በእርሳቸው ጋር ብቻ ሳይሆን በአካባቢያቸው ከሚኖረውና የበላይነት ካለው የአማራ ኅብረተሰብ ጋርም ነው። የቅማንት ኅብረተሰብ ከአማራው ሕዝብ ጋር ስላለው ትስስር በዚህ ምዕራፍ የሚገለጽ ሲሆን በተጨማሪም ስለቅማንት ቤተሰብና የሃይማኖት ሥርዓት ይታያል። ስለቅማንት አገር (መሬት) ግልጽ የሆነ ግንዛቤ ማግኘት ስለሚገባ በቅድሚያ ስለመልክአ ምድሩ እንመለከታለን።

## መልክአ-ምድር

ኢትዮጵያ ብዙ የተለያየ የአየር ጠባይ ያለው የመልክአ ምድር አቀማመጥ ያላት ሲሆን በጣም የታወቀው ግን ደልዳላው የደጋ ክፍል ነው። የእንቁላል ቅርጽ ያለው የደጋ ክፍል ከሰሜን ወደ ደቡብ ምዕራባዊ አጋማሽ 900 ማይል፣ ከምሥራቅ ወደ ምዕራብ ደግሞ ሰፊ በሆነው አቅጣጫ በኩል 500 ማይል ርዝመት አለው። ከባሕር ወለል አማካይ ከፍታው 7000 ጫማ ሆኖ ደጋው አገር ከደቡብ በኩል በስተቀር ዙሪያውን ቀጥ ባለ ገደላ-ገደል የታጠረ ነው። በደቡብ በኩል ግን ቀስ እያለ እያሽቆለቆለ የሚወርድ ጉራንጉር መልክአ–ምድር ነው ያለው። በደጋው ዙሪያ ሠንበሌጥ ሣር የሚያድግበት፣ በክረምት ወራት ደግሞ ረግረጋማ የሆነ መሬት፣ በከፊል ደግሞ መለስተኛ ምድረ በዳና ጨርሶ ምድረ በዳ የሆነ መሬት እንደቀለበት ከብቦት ይገኛል። ሚዳዎች፣ ሰንሰለታማና ደልዳላ ተራራዎች የዚህ ክፍል መልክአ-ምድር ዋና ዋናዎቹ ገፅታዎች ናቸው። እንደተከዜና አባይ በመሰሉ ጉድጓዳ ሸለቆዎች፣ ሌሎች ወንዞችና በመቶዎች የሚቆጠሩ ትናንሽ ጅረቶች ደጋው ክፍል የተሸነሸነ ነው። የዝናቡ ወራት ከሰኔ እስከ ጥቅምት ወር የሚጠናከር ሲሆን በየዓመቱ ከሠላሣ እስከ ሰማንያ ኢንች ዝናብ በአካባቢው ይጥላል።

ይህ የተቆራረጠ መልክአ-ምድር፣ ምሽግ የመሰሉት ገደላ-ገደል፣ በጊዜ ብዛት በወንዞች ሸርሸራ የተፈጠሩት ጉራንጉሮችና ሸለቆዎች ለዘመናት የውስጥና የውጭ ግንኙነቶችን ገድበው እንደቆዩ እንረዳለን። መልክአ-ምድሩ ጉድጓዳ ሆኖ በመቆየቱ

ከውስጥም ሆነ ከውጭ፡ በወረራም ሆነ በስደት ወይም በሌላ መልክ የባህል መቀላቀልና ውሕደት እንዳያፈጽም እንቅፋት ሆኖ ቆይቷል። በሌላ መልኩ ደግሞ ይህ ሁኔታ ኢትዮጵያ ለዘመናት ታሪኳንና ነፃነቷን ጠብቃ፡ በአካባቢው ራሱን የቻለ የፖለቲካ ኃይል ሆና እንድትቆይ ያስቻላት ከመሆኑም በላይ የተለያዩ የኅብረተሰብ ክፍሎች የተለያዩ ባህሎቻቸውን ይዘው እንዲኖሩ ረድቷቸዋል። በእርግጥ ባለፈው አንድ ሺህ ዓመት ሌሎች ሕዝቦችና ባህሎቻቸው የደጋውን አጥር ጥሰው ሠርገው በመግባት በአገሩ የተንሸራሸሩ ቢሆንም የባህል መቀላቀል እንዲደረግ የአገሪቱ መልክአ-ምድር አላስቻለም።

የቅማንት አገር (መሬት) በሰሜናዊ ምዕራብ ደጋማው ጉራንጉር በኩል ከጣና ሃይቅ በስተሰሜን 18 ማይል ርቆ የሚገኝ ሲሆን ከፍታው ከባሕር ወለል ከ4000 እስከ 10000 ጫማ ይደርሳል። ወርድና ስፋቱን ስንመለከት ደግሞ ቅርጹ በሁሉም በኩል እኩል ባይሆንም በግምት 30 ማይል በ50 ማይል ይሆናል።

የቅማንት አፈ-ታሪክ እንደሚነግረን ድሮ የመጀመሪያዎቹ ሰፋሪዎች ሲመጡ መሬቱ በደን የተሸፈነ እንደነበር፣ ነገር ግን ዛፎች እየተጨፈጨፉ መሬቱ ለዘመናት ሲታረስ በመኖሩ አሁን አገሩ ስለተራቆተ ሰብል ከተሰበሰበ በኋላ በበጋው ወራት የገጠጠ ጠፍ መሬት መስሎ ይተያል። አልፎ አልፎ ግን እንደግራር፣ ወይራ፣ ብሳና፣ ዋርካ፣ ዶቅማ የመሳሰሉት ዛፎች በአካባቢው አሉ። እንዲሁም አንዳንድ የማይታረሱና የሃይማኖት ሥነሥርዓት የሚካሄድባቸው ድግናዎች ተጠብቀው የቆዩ የተፈጥሮ ደኖች አሉአቸው። በቆላማው አካባቢ በተሻለ ሁኔታ በርካታ ዛፎች በተለይም ግራር በብዛት ይታያል። በአስራ ዘጠነኛው መቶ ዓመት መገባደጃ ላይ ከአውስትራሊያ የመጣው የባሕር ዛፍ ዝርያ ተስፋፍቶ በአንዳንድ መኖሪያ ቤቶች አካባቢ ለግንባታ ሥራ የሚያገለግሉ ከሃያ እስከ ሰላሣ የሚሆኑ ዛፎች ማየት የተለመደ ነው።

አእዋፍን በተመለከተ ኃይለኛ ዓይን ያላቸው ጭልፊቶች በቅማንት መኖሪያ አካባቢ ትልቁን ቀይ ክንፋቸውን ዘርግተው ከፍ ብለው ሲያንዣብቡና አስፈላጊም በሆነ ወቅት ምግብ ፍለጋ ወደ መሬት በመወርወር ከመቅጽፈት አይጥ ወይም ጥንቸል በጥፍ ራቸው አንጠልጥለው ሲሄዱ ይታያሉ። በሌላ ጊዜ ደግሞ

ከትላልቆቹ ጅረ አሞራዎች ጋር በሞተ እንስሳ አስከሬን ላይ ሲፋተጉ ይውላሉ። በቀይ፣ በቢጫ፣ በሰማያዊና በአረንጓዴ ተሰተ ደመና ቀለም ያሸበረቁ ትናንሽ አእዋፋት በዛፎች ውስጥ ሲሽሎኮሎኩና በመሬት ደግሞ ሲያኮበኩቡ ማየቱ ድንቅ ትርኢት ነው።

ወደ ምዕራቡ ዳርቻ ካልሆነ በስተቀር እዚህ ትላልቅ አውሬ እንስሳት በቅማንት መሬት አካባቢ አይገኙም። ጠፍ በሆኑ ስፍራ ቦታዎች ሚዳቋ ቢገኝም ድኩላ፣ አነር፣ ምስጡ-በል (አውጭ) ፣ የዱር አሳማና ባለነጠብጣብ ጅብ በጣም ውስን በሆነ ቦታና ጊዜ ይታያሉ። በዓለም ብርቅዬ ከሆኑት የዱር እንስሳት አንዱ የሆነው ዋልያ በጣም ከፍ ካለውና ጉራንጉር ከሆነው በቅማንት ሰሜናዊ ክፍል እንደሚገኝ ይነገራል።

በቅማንት አካባቢ በጣም በብዛት የሚገኘው የዱር እንስሳ ደግሞ ዝንጀሮ ነው። ሕዝቡ ዝንጀሮዎችን እያሳደደ በድንጋይ ስለሚውግራቸው የሞተ ዝንጀሮ በየቦታው ማየት የተለመደ ነው። «ሰብላችን ስለሚያወድሙብን እኛም ተከታትለን እናወድማቸዋለን» የሚል አስተያየት ነው ከሕዝቡ የሚሰማው።

በአካባቢው ሦስት ዓይነት የዝንጀሮ ዝርያዎች ይገኛሉ። አንደኛው ዓይነት ዝንጀሮ አይን የሚማርክ መልክ ያለው ባለጥቁርና ነጭ ቀለም፣ ለስላሳ ፀጉር ያለውና ባለነጭ ጭራ ጉሬዛ ነው። ጉሬዛ ፍራፍሬና ቅጠለ-በል ሲሆን አብዛኛውን ጊዜ በዛፎችና በጫካ ውስጥ ተደብቆ ስለሚውል አልፎ አልፎ በአጋጣሚ ነው የሚታየው። ሁለተኛው ደግሞ በብዛት የሚታየው ጦጣ የተባለው የዛፍ እንስሳ ነው። ነገር ግን በአሁኑ ጊዜ አብዛኛው ዛፍ ተቆርጦ ያለቀ በመሆኑ ጊዜውን የሚያሳልፈው ሰብል በማውደም ነው። ሦስተኛውና የመጨረሻው የዝንጀሮ ዝርያ ጉራንጉር በሆነው ቆላማ አካባቢ የሚገኘው ግመሮ የሚሉት ዝንጀሮ ነው። ብዙውን ጊዜ በመንጋ የሚታይና በአውራጃው ከሚገኙ ማንኛውም የገጠሬ ውሻ ቁመናው የገዘፈ ነው። በመሆኑም ከተንኩ መልሰው በከፍተኛ ብዛት በመሰባሰብ ለማጥ ቃት ስለማይመለሱ ገበሬው እነዚህን የዝንጀሮ ዝርያዎች መሬቅ እንጂ በድንጋይ ለመውገር አይደፍርም።

በበጋ ወራት በዓጣ መኢፌቴት፡ በዝናቡ ወራት ደግሞ ከአንድ እስከ ሁለት ሜትር እርዝማኔ ባላቸው ዓጣዎች ወንዞች

በበጋው ወራት ድንጋማ መሬት በቅማንት አገር በበሬ ሲታረስ።



ስለሚሞሉ አርጃኖ (ዓሣዘበል) በተባለው እንስሳ ይዘወተራሉ:: ዓሣው ናይል ፐርች የተባለው ዝርያ ሲሆን ወንዞች በሚሞሉበት በክረምት ወራት ከጣና ሐይቅ በመነሣት ወንዞችን ተከትሎ ወደ ቅማንት አካባቢ ይመጣና እንቁላሉን ጥሎ የክረምቱ ወራት ማለቂያ ላይ እንደገና ተመልሶ ወደ ጣና ይወርዳል::

ምንም እንኳን የቅማንት መሬት ድንጋያማና ወጣ ገባ ቢሆንም አፈሩ የእሳተ ጎመራ አመድ-ቀመስ በመሆኑ በጣም ለም ነው:: መካከለኛ የሆነ ጥሩ የአየር ጠባይና ከሚያዚያ ወር እስከ ጥቅምት ወር ድረስ የሚጥለው ዝናብ 50 ኢንች ስለሚደርስ ለግብርናው ሥራ በጣም የተስተካከለ ሁኔታን ይፈጥራል:: ሁለት የዝናብ ወቅቶች አሉ:: አንደኛው የበልግ ወራት (ትንሹ ዝናብ) በሚያዚያ ወር ዝናብ ይጥላል:: አንዳንድ ጊዜም ከየካቲት ወር ጀምሮ እስከ ግንቦት ወር ድረስ የሚጥልበት ወቅት አለ:: ከጥቂት ዓመታት ወዲህ ግን የበልግ ዝናብ እየቀረ ነው:: የግንቦትና የሰኔ ወራት ብዙውን ጊዜ ድርቅ ቢሆንም በሁለተኛው የዝናቡ ወቅት በሐምሌና በነሐሴ ወራት ዶፍ ዝናብ ይወርዳል:: የአብዛኛው የቅማንት መሬት አማካይ የአየር ሙቀት ከ60$^0$ እስከ 70$^0$ ዲግሪ ፋራንሃይት ስለማይበልጥ አካባቢው የማይቋረጥ የፀደይ ወቅት ያለው ይመስላል::

አንቀሳፍተው የነበሩት ትናንሽ ወንዞች በክረምት ወቅት በጣም በደፈረሰ ውሃ ተሞልተው መደንፋት ይጀምራሉ:: ያኔ ከአንድ ቦታ ወደ ሌላ ቦታ መሄድ አስቸጋሪ ስለሆነ የውስጥ ግንኙነት ሁሉ ይቋረጣል:: ይህንንም በመገንዘብ በክረምቱ ወቅት የአረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖታዊ ሥነሥርዓቶች አከባበር እቅድ አይኖርም:: በዚህ ወቅት ሰማዩ ይጠቁራል፣ ተራሮችና ሸለቆዎች ደብዛዛና ቡናማ ገጽታ ይኖራቸዋል:: በክረምቱ አጋማሽ ላይ የተዘራው ሰብልና የተፈጥሮ ሣር ማቆጥቆጥ ይጀምራል:: ከመስከረም ወር ጀምሮ ሰማዩ ጠርቶ ፀሐይ ሙቀትዋን ስትለግስ አካባቢው በሙሉ በአረንጓዴ ምንጣፍ የተሸፈነ ይመስላል:: ከዚያም ተቋርጦ የነበረው ግንኙነት እንደገና ተስተካክሎ የሰብል ስብሰባ ወቅት ይመጣል:: የበጋው ወቅት እየተቃረበ ሲመጣ የአገሩ አካባቢ ወደ አፏራማና ቡናማ ቀይ ይለወጣል:: ይህም ሁኔታ የበልጉ ዝናብ እስኪመጣ እንዳለ የሚቆይ ይሆናል::

የትግንት የአካባቢ ሁኔታ ከአብዛኛው የኢትዮጵያ ደጋ ክፍል ጋር የሚመሳሰል ስለሆነ እንደሚከተለው በተለያዩ ዞኖች ተመድቦ እናገኘዋለን::

1. ቆላ:- ከባሕር ወለል መንሻ እስከ 7000 ጫማ ከፍታ ላይ ይገኛል:: ከሞቃታማነት እስከ ማቃጠል የሚደርስ የአየር ጠባይ ያለውና ብዙውን ጊዜ በበሽታ የሚጠቃ ነው:: በክረምት ወቅት አንዳንድ አካባቢዎች ዝናብ ያገኛሉ:: ዝርያውና መሠረቱ የሰሜንና ማዕከላዊ ኢትዮጵያ የሆነው ጤፍ፥ ዘንጋዳ፣ ዳጉሣና ጥጥ የአካባቢው መሰረታዊ ምርቶች ናቸው::

ሀ. በረሃ የሚባለው ከቆላማ ቦታዎች ሁሉ በጣም ሞቃት የሆነው ነው:: ቶሎ የሚያድግ ሣር የሚገኝበትና ለሰደድ እሳት (ቋያ) የተጋለጠ መሆኑ ሲታወቅ ለጤን ነት እጅግ በጣም አደገኛ አካባቢ ነው::

ለ. ምድረ-በዳ:: እውነተኛው ሙሉ በሙሉ በረሃ የሆነ አካባቢ ነው:: በረሃ የምንለው ግን መለስተኛ ምድረ-በዳነት ጠባይ ያለውን ነው::

2. ወይና ደጋ:: ከ6000 እስከ 9000 ጫማ ከፍታ ላይ የሚገኝ አካባቢ ነው:: አየሩ መካከለኛ ሞቃትና ቅዝቃዜ ያለው ሲሆን እንደ ቀይ ጤፍ፣ ስንዴ፣ ገብስና አተር ይመረትበታል::

3. ደጋ: ከ8000 እስከ 15000 ከፍታ ላይ ይገኛል:: የአየሩ ጠባይ ከቦታ ቦታ የሚለያይ ቢሆንም በአብዛኛው ቀዝቃዛ ና ብርዳም ነው:: ዋናው የአካባቢው ሰብል ገብስ ቢሆንም እንደ ምስር፣ ተልባ፣ ባቄላ የመሳሰሉት ይመረታሉ:: አልፎ አልፎ ውርጭ ሰብሉን ሊያጠቃ ይችላል:: ሎቄ የሚባለው ደግሞ በዚሁ ዞን በ12000 እስከ 15000 ከፍታ ላይ የሚገኘው የመጨረሻው ብርዳም የደጋው ቁንጮ ነው:: እርሻ አይታረስበትም ሆኖም በመጠኑ ለከብቶች ገጠሽ ይጠ ቀሙበታል:: ራስ ዳሽንና የጉና ተራራዎች ትክክለኛ ወካይ ምሳሌዎች ናቸው::

የተገለፁት ክፍታዎች በሚገባ የተለዩ ሳይሆን ለዞኖች መለያ እንዲረዳ ተብሎ በአየሩ ጠባይ፣ በሚያበቅሉት አዝርዕትና ሰዎች ባላቸው ግንዛቤ ላይ የተመሠረተ ነው። ይህም በመሆኑ አንድ ደጋ ወደ ወይናደጋ ሲወርድ ወደ ቆላ ወረደኩ ይላል ምክንያቱም እሱ ከተለማመደው አየር ጠባይ ሞቃት ሆኖ ስለሚያገኘው ነው። በእርግጥ ቆለኞች የእነሱ አካባቢ «ከሌላው ዓለም የተሻለ ነው» ብለው የሚያምኑ አሉ ብሎ ደፍሮ መናገር ባይቻልም ይህን ግን እውነት ነው ብሎ የሚቀበሉ ቆለኞች አይጠፉም። አብዛኛው የቅማንት ሕዝብ የሚኖረው በወይና ደጋው አካባቢ ሲሆን ከፊሉቹ ደግሞ በቆላና በደጋ ይኖራሉ።

## በቅማንትና በኢትዮጵያ ያለው ትስስር

የቅማንት ሕብረተሰብ ከጥንት ጀምሮ ከአበሻ ጋር ተሳስሮና ተሰባጥሮ፣ ከዚያ ቀጥሎም በአስተዳደርና በኢኮኖሚ ሰንሰለት ከኢትዮጵያና ከሕዝቧ ጋር ተቆራኝቶ የኖረ በመሆኑ ግንኙነቱ ጥንታዊ ነው። ዛሬ በሌሎች የኢትዮጵያ ጐሣዎች ላይም እንደሚፈፀመው ሁሉ የአማራውና የትግሬው ባላባታዊ የገዥ መደብ ቅማንቱንም ተቆጣጥሮ እያስገበረ ይገኛል።

ይህ የባላባታዊ አቋም ቀስ በቀስ ወደ ዘመናዊ ኢንዱስትሪያል የከተማ አስተዳደር እየተሸጋገረ ቢሆንም ቅማንቶች በአሁኑ ወቅት በዝቅተኛው ፊውዳላዊ የሥራ ደረጃ ስለሚገኙ ቀጥታ ግንኙነታቸው ከባላባታዊ የአስተዳደር ወኪል ጋር ነው። ዝቅተኛ የሆኑት የቅማንት አካባቢ የአስተዳደር ሥራዎች በባህል ለውጥ ወደ አማራነት በተለወጡ ወይም በጦር ሜዳም ሆነ ወይም በሌላ መልክ ከአማራው ጋር የተቆራኙ የቅማንት ሹማምንት የተያዙ ናቸው።

በኢትዮጵያ አምስት የመንግሥት የአስተዳደር እርከኖች አሉ። እነሱም፦ ንጉሠ ነገሥታት፣ ጠቅላይ ግዛት፣ አውራጃ፣ ወረዳና ምክትል ወረዳ በመባል ይታወቃሉ። እስከ 1850ዎቹ ዓ.ም. የንጉሠ ነገሥታቱ መናገሻ ዋና ከተማ ሆና የቆየችው ጐንደር አሁን ደግሞ የቤጌምድርና ስሜን ጠቅላይ ግዛት ዋና ከተማና የ13000 ነዋሪዎቿ የገበያ፣ የሃይማኖትና የትምህርት ማዕከል ናት። ጐንደር በአየር ከሌሎች ዋና ከተሞች ጋር ትገናኛለች ። በየብስ ደግሞ ከከተማው ወደ ሰሜንና ወደ ደቡብ

በሚወስደው የጠጠር አውራ ጉዳና አማካይነት ግንኙነት ታደርጋለች።



ከአዘዞ ወደ ጭልጋ የሚወስደው መንገድ ጓንግ ወንዝ አካባቢ ሲታይ። አካባቢው ቆላማ ነው።

የቅማንት ሕዝብ መኖሪያ አካባቢ በጓንግ ወንዝ ከሁለት የተከፈለ ነው። ከአንዳንድ የአነጋገር ዘይቤዎችና ባህላዊ ሥነሥርዓቶች አፈጻጸም በስተቀር ተመሳሳ ይነት አላቸው። ይህም አከፋፈል በቅማንት የሃይማኖትና ፖለቲካ አደረጃጀት ታዋቂነት የነበረውና በተተኪው የአማራው ባላባታዊ አስተዳ ደርና በአዲሲቱ ኢትዮጵያ የአውራጃዎች ድንበር አከላለልም ተቀባይነት አግኝቶ ተግባራዊ የሆነ ነው። በመሆኑም ግማሹ የቅማንት መሬት በጎንደር አውራጃ ሥር ሆኖ አመራሩን ከጎንደር ከተማ የሚቀበል ሲሆን ሌላው ደግሞ በጭልጋ አውራጃ ሥር ሆኖ በምስራቁ ክፍል ከምትገኘው አይከል ከተባለችው አነስተኛ ከተማ አመራር ያገኛል።

የቅማንትን ሕዝብ ከሌላው ጋር የሚያስተሳስረው ሌላው ጉዳይ ደግሞ የአካባቢው የገበያ ሥርዓት ነው። የቅማንት ሕዝብ የሚያመርታቸውን የግብርና ውጤቶች ከፊሉን እቃ በእቃ በአካ ባቢው ካለው ሕብረተሰብ ጋር ይለዋወጣል፣ ቀሪውን ደግሞ ጎንደር ገበያ ወስዶ ይሸጣል። በጎንደር ዙሪያ የሚኖሩ የከርከር ቅማንቶች ጭልጋ ካሉት ቅማንቶች የበለጠ ከጎንደር ከተማ ሕዝብ ጋር ይገበያያሉ። ባለፉት ሰላሣ ዓመታት ለጎንደር ከተማ የተሸጡ -ት የእርሻ ውጤቶቸ አልፎ ተርፎ ወደ ሌሎች የኢትዮጵያ ዋና ከተሞቸ ገበያዎች ይተላለፉና ከብሔራዊ ፍጆታ የሚተርፈው ቀሪው ደግሞ ለዓለም ገበያ የሚቀርብበት ጊዜ አለ። በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን መጨረሻ ላይ በተፋጠነ መልክ በባህል ለውጥ ወደ አማራነት የመለወጡ ሂደት እየተጣደፈ በመጣበት ወቅት ቅማንቱን ወደ ብሔራዊ ጥልፍልፍ ውስጥ የሚያስገባ ሦስተኛውና መሠረታዊ የሆነ ሁኔታ ተፈጥሯል። ይኸውም የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተክርስቲያን ስትሆን በአሁኑ ጊዜ በማንኛውም የቅማንት ኅብረተሰብ ውስጥ ቤተክርስቲያንና ቀሳውስቱ ስር ሰደዋል።

## ኅብረተሰቦች

ጥናቱ የተመሠረተው በከርከርና በጭልጋ በሚገኙ ሁለት ኅብረተሰቦች ላይ በተደረገ የመስክ ጥናት ነው። ሁለቱ ቦታዎች በአረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖትና በፖለቲካ ማዕከልነታቸው የታወቁ ከመሆኑም በላይ ሁሉንም የቅማንት ማኅበረሰብ ይወክላሉ። ከርከር በወይናደጋነቷ የታወቀች ቢሆንም በስተሰሜን በኩል ቆለኛና ደገኛ

ቅማንቶች የሚኖሩበት አካባቢ አለ፡፡ ጭልጋ ደግሞ በወይናደጋና በቆላው ዞን ይመደባል፡፡ ማሲያኖች እንደለኩት በከርከር የመጨረሻ ከፍ ያለው ቦታ ከባሕር ወለል 8873 ጫማ፣ ዝቅተኛው ክፍል ደግሞ 6500 ጫማ ነው፡፡ ጭልጋ የመጨረሻው ከፍተኛ ቦታ ከባሕር ወለል 6732 ጫማ ነው፡፡ (ኮንሶዚዮን ቱሪስቲካ ኢታሊያና 1938፣232፣362)፡፡

አስቀድሞ እንደተጠቀሰው ቅማንቶች የሚኖሩት በተበታተኑ ሠፈራዎች ሲሆን የከርከርና የጭልጋ ሁኔታም ከዚህ የተለየ አይደለም፡፡ በእርሻ ላይ ያሉት ሠፈራዎች ከአንድ እስከ አራት የሚደርሱ ቤቶች በአንድ ላይ ያሉበትና በተመሳሳይ ሁኔታ ሌሎች ቤቶችም ከ300 ሜትር እስከ 3000 ሜትር በሚደርስ አንዱ ከሌላው ተራርቀው ይገኛሉ፡፡ በመሠረቱ መንደር የምንለው ከ10 እስከ 20 የሚደርሱ ቤቶች ጠፍ በሆነ ቦታ ላይ ተሰብስበው የተገኙ እንደሆነ ነው፡፡ በቅማንት ኅብረተሰብ ግን ይህ አይታወቅም፡፡ ጆርጅ ፒ. መርዶክ እንዳለው የቅማንት ሕብረተሰብ ቤተሰቦች አንዱ ከአንዱ ተራርቆ በከፊል በመገለል በጉርብትና የሚኖሩ እንጂ በመንደር የተሰባሰቡ አይደሉም፡፡ በከርከርና በጭልጋ እንዲሁም በሌሎች ቦታዎች እንደሚታየው ሁሉ የታረሱ መሬቶች፣ ያደሩ መሬቶች፣ የግጦሽ መሬቶችና ቁጥቋጦዎች በረድፍ ሥነሥርዓት ይዘው ይገኛሉ፡፡ በእነዚህ ቦታዎች ደግሞ አልፎ አልፎ ጣልቃ ገብ ሆነው አሠራራቸው በተለይ የቅማንቶች ስልት ነው ተብለው የታወቁት የእንቁላል ቅርጽ ወይም ክብ የሆነ፣ ግድግዳቸው ጨፈቃና የጭቃ ምርጊት ሆኖ የሣር ክዳን ቤቶች ይታያሉ፡፡ በአጭሩ በኅብረተሰቡ መካከል ያልተያዘ ስፊ ቦታ አይገኝም፡፡

አንዱ ኅብረተሰብ ከሌላው ኅብረተሰብ ሰው ሠራሽ በሆኑ ወይም የተፈጥሮ ድንበሮች ተከልለው ይገኛሉ፡፡ ቅማንቶች በጥንታዊ ባህላቸው መሠረት ርስታቸውን ተካፍለው ይኖራሉ፡፡ ይህም ሁኔታ ከቅርብ ጊዜ ወዲህ ከተቋቋሙት የቤተክርስቲያን ሥነሥርዓትና ከመንግሥት የአስተዳደር ተወካዮች ጋር የሚያጋጭ አይደለም፡፡ ሁሉንም ቅማንት ደግሞ አስተሳስሮ የቆየው በአንድነት ላይ ሆነው የሚያከብሩት የአረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖት ክብረ-በዓል ነው፡፡

ዝርዝር ጥናቱ የተካሄደው በሰንሰለታማ ተራራዎችና ገደላገደል ተከፋፍለው በከርከር በሚገኙ ሦስት ንዑስ ኅብረተሰቦች

ላይ ነው። ዋናው ጥናት የተካሄደበት በተለይ ከርክር አንቻው ሚካኤል ይባላል። ይህ ቦታ የጥቁር አባይና የተከዜ ወንዞች ተፋሰሶች መለያና መሸጋገሪያ በር መሆኑ ይታወቃል። ወደ ጉንደር የሚወስደውና የሁለቱንም ወንዞች ተፋሰስ የሚያሸጋግረው የእግር አውራ ጉዳና አሁንም ከዘመናት አገልግሎት ከኋላ በዚህ አልፎ ይሂዳል። የከርክር ሕዝብ ብዛት እ.ኤ.አ. በ1965 ዓ.ም. 2640 ሲሆን በተለይ የአንቻው ሚካኤል ሕዝብ ደግሞ 650 ነበር። የደቡብ ምሥራቅ የከርክር ጫፍ ከጉንደር ከተማ በእግርም ሆነ በተሽከርካሪ ጣሊያኖች በሠሩት መንገድ ስድስት ማይል ወጣ ብሎ ይገኛል። (በመጽሐፉ የመጀመሪያው ሽፋን ያለውን ካርታ ይመልከቱ)። የእኔዋ ትንሿ ቮልስዋገን መኪና ከአሁን በፊት ሌላ መኪና አይቶት ስለማያውቅ አንዳንዴ እየተነዳች፥ ሌላ ጊዜ ደግሞ በግፊና በሽክም ነበር መንገዱን ያገባደደችው። መንገዱ ሁለት ማይል ተኩል ያህል ወደ ምዕራብ አቅጣጫ ከሄደ በኋላ ወደ አንቻው ሚካኤል አፋፉን ያህል እንደዘለቀ ይቋረጣል። ከዚህ መንገድ ተገንጥሎ 12 ማይል ያህል ሰሜናዊ ምዕራብ አቅጣጫን ተከትሎ የሚሄድና ከከርክር ሰሜናዊ ትሪያንግል ጫፍ የሚገናኝ መንገድ ይገኛል። ሌላው በጣሊያኖች ተሰርቶ ለብዙ ዘመን ከተተወ በኋላ እ.ኤ.አ. በ1965 ዓ.ም. ተጠግኖ በበጋው ወራት አገልግሎቱ እንዲቀጥል የተደረገ መንገድ አለ። ምንም እንኳን እነዚህ የመገናኛ መስመሮች ቢኖሩም ከከርክርና ከሌሎች ቦታዎች ወደ ጉንደር የሚደረጉ ግንኙነቶች በእግር፥ በአህያና በበቅሎ ነው።

ዝቅተኛው የመንግሥት አስተዳደር እርከን የከርክርና ዋላጅ ምክትል ወረዳ ሲሆን በአማራና በቅማንት ሹማምንት ይመራል፥ ነገር ግን በከፍተኛ ደረጃ ያሉት የወረዳውና የአውራጃው ጽሕፈት ቤቶች ጉንደር ከተማ ነው የሚገኙት።

ሁለተኛው ጥናት የተካሄደበት ቦታ ደግሞ ከከርክር በሕዝብ ብዛት ይበልጣል። ከጉንደር ወደ ደቡብ አቅጣጫ ለ6 ማይል ያህል በአውራ ጉዳና ከተጓዙ በኋላ እንደገና ወደ ሰሜን አቅጣጫ አነስተኛ መኪና በሚያስኬድ መንገድ ጉዞ በመቀጠል የጓዋንግ ወንዝን ተሻግሮ የጭልጋ ማዕከል ይገኛል። ወንዙ በሚቀንስበት ወራት የመንግሥት ላንድሮቨር መኪናዎችና የአንድ ነጋዴ የጭነት መኪና ስለሚመላለሱበት በመጠኑም ቢሆን መንገዱ ደህና ነው። የጭልጋ ኅብረተሰብና የጭልጋ ወረዳ ድንበሮች እዚህ

ላይ ይገጣጠማሉ:: ለጭልጋ ወረዳ፡ አውራጃና ለአካባቢው የአስተዳደርና የገበያ ማዕከል ሆነው የሚያገለግሉ ሁለት ከተሞች ቅርብ ለቅርብ ይገኛሉ:: እነዚህ ከቅርብ ጊዜ ወዲህ የተቆረቆሩት ከተሞች በአብዛኛው በቅርብ ጊዜ የመጡ ነዋሪዎቻቸው ቅማንት ያልሆኑ ቢሆንም ከዚህ ላይ ሊነሡ የቻሉት ስለጭልጋ ኀብረተሰብ የተሟላ ግንዛቤ እንድናገኝ ስለሚረዳ ነው:: «ጭልጋ» የሚለው ስያሜ ከመሠረታዊው የቅማንት ሕብረተሰብ ይዞታ አሁን ሰፋ ያለ በአማራው መንግሥት የተፈጠረ የአስተዳደር ዘርፍ ነው::

ከሁለቱ ትናንሽ ከተሞች ላቅ ያለው አይከል የአውራጃው አስተዳደር ማዕከል ናት:: ከተቆረቆረች 35 ዓመት የሚሆናት ይህች ከተማ 800 ያህል ሕዝብ ይኖርባታል:: በመንግሥቱ ጽሕፈት ቤት ግቢ ውስጥ ጥንታዊ የአማራ ዓይነት የድንጋይ ቤቶች አሉ:: የአካባቢው የጥንት ዓይነት ቤቶች ቅርጻቸው አራት ማዕዘን፣ ግድግዳቸው እንጨትና ጭቃ የሆኑ የቆርቆሮ ክዳን ባላቸው ዘመናዊ ቤቶች እየተተኩ ነው:: በአዲስ መልክ ከተሠሩት ቤቶች መካከል በርካታ መሸታ ቤቶች፣ አንድ ምግብ ቤት፣ ሱቆች፣ አንድ አነስተኛ አንደኛ ደረጃ ትምህርት ቤትና ከጐንደር ከተማ ጋር የሚያገናኘው የስልክ ቤት የመሳሰሉት ይገኙበታል:: የጭልጋ ወረዳ የአስተዳደር ማዕከል የሆነችው ሠራባ ደግሞ አንድ መቶ ያህል ሕዝብ የሚኖርባት መንደር ናት:: ከተመሠረተች ሃያ ዓመት የሚሆናት ይህች መንደር ቁጥራቸው አነስተኛ ከሆነው ዘመናዊ ቤቶችና በኮንክሪት ከተሠራው አንድ አንደኛ ደረጃ ትምህርት ቤት በስተቀር ሌሎቹ የጥንት ዓይነት የሣር ቤቶች ናቸው::

ከከርከር በስተሰሜን በቅርቡ የአስተዳደርና የገበያ ማዕከል ሆና የተመሠረ ተችው ትክል ድንጋይም በአዲሱ ስልት የተሠሩ ሕንፃዎች አሏት:: አይከል፣ ሰራባና ትክል ድንጋይ ብቻ ናቸው በቅማንት አካባቢ የሚገኙት አነስተኛ ከተሞች:: የቤት አሠራራቸው ከጥንቱ የአካባቢው የቤት አሠራር ዓይነት የተለየ ነው:: ከነዚህ ከተሞች በስተቀር በሌሎች የቅማንት አካባቢዎች አዲሱ የቤት አሠራር አይታወቅም::

በአይከልና በሠራባ መካከል የብሔራዊው ሕዝባዊ ኑሮ እድገት ሚንስቴር ጣቢያ ይገኛል:: በሠራባ የሚገኘው አንደኛ ደረጃ ትምህርት ቤት በዘመናዊ የምዕራባዊ አርኪቴክቸርና

ዲዛይን፣ እና በውጭ ሀገር ፋብሪካ በተመረቱ ቁሳቁሶች (ከቆርቆሮ ክዳን በስተቀር) የተሠራው በቅማንት አካባቢ የሚገኘው ብቸኛ ሕንፃ ነው::

## መኖሪያ ሠፈርና ቤታቸው

እንደ ብረት የጠነከሩት የስልሳ ዓመት አዛውንቱ የአቶ ረዳ ቤት ዓይነተኛውን የቅማንት ቤት ይወክላል:: አንድ ሺ ሜማ አለፍ ብሎ ደግሞ የታናሽ ወንድማቸው የአዮ ቤት ይገኛል:: የአቶ ረዳ ቤተሰብ፣ ሁልጊዜ ደስተኛና ወፈር ያሉትን ሃምሣ ዓመት ዕድሜ ያላቸውን ባለቤታቸውን ወይዘሮ አዳነችን፣ የሃያ ዓመት ዕድሜ ያለውን ሎጋና ያላገባውን ልጃቸውን መልኬንና የአልጋ ቁራኛ የሆኑትን የሰማንያ ዓመት ሽማግሌ አባታቸውን አቶ አየነውን ያካትታል:: ዕድሜያቸው እንደቅደም ተከተላቸው ሠላሣ አምስትና ሠላሣ ዓመት የሆነው ደንዳና ልጆቻቸው ነጋሽና ቢተው ሚስት አግብተው ጎጆ በመውጣት ከአባታቸው ቤት አጠገብ ቤት ሠርተው ይኖራሉ:: ይህ በአርሻ መካከል የተመሠረተው ሠፈራ ሶስት ተቀራርበው የተሠሩ ቤቶችንና ለልዩ ልዩ አገልግሎት የተሠሩትን ትናንሽ ጎጆዎችን ያጠቃልላል::

እንደሌሎች የአገሬው ቅማንት ቤቶች የአቶ ረዳ ቤት ግድግዳው ጨፈቃና በጭቃ የተመረገ ሆኖ ጣራው የሣር ክዳን ነው:: ሁለት ዓይነት የጣሪያ ቅርጽ በቅማንት ሀገር የተለመደ ሲሆን በብዛት የሚገኘው የእንቁላል (ሽሙልሙል) ቅርፅ ያለው ነው:: ሌላው ደግሞ እምብዛም በብዛት ባይታይም ክብ የሆነው የጣራ ዓይነት ነው:: የአቶ ረዳና የቢተው ቤቶች የእንቁላል ቅርፅ ያላቸው ሲሆን አስራ አምስት በሃያ አራት ሜማ በሆነ ቦታ ላይ አርፈዋል:: የነጋሽ ቤት ግን ክብ ሆኖ መሀል ለመሀል ዙሪያውን 22 ሜማ ነው:: ጣሪያውም የእንቁላል ቅርጽ የሚመስለው ቤት ሁለት ምሰሶዎቸ ብቻ ሲኖረው ክብ የሆነው ግን መሀል ላይ የተተከለ አንድ ወጋግራ (ምሰሶ) ወይም ቤቱ ትልቅ ከሆነ አራትና ከዚያም በላይ የሆኑ ወጋግራዎች (ምሰሶዎች) መሀል ለመሀል ዙሪያውን ይቆማሉ:: ክብ የሆነው ቤት ሾጣጣ ጣሪያና አንድ ጉልላት ሲኖረው ሽሙልሙል ቅርጽ ያለው ቤት ደግሞ በዚያው ልክ ቅርፁን ይዞ ወደላይ ከፍ ይልና በመጨረሻ ላይ ሶስት ሜማ ስፋት ያለው ድምድማት ይኖረዋል:: ሁለቱም ዓይነት ቤቶች

ለአየርና ለብርሃን ማስገቢያ ጭምር እንዲያገለግል ከቋሚ እንጨት ጋር በማጠፊያ የተያያዘ አንድ የእንጨት በር ብቻ አላቸው።

አቶ ረዳም ሆኑ ሌሎች ግለሰቦች ባለ ሁለት ምሰሶው ቤት የበለጠ ተወዳጅነት እንዳለው ይናገራሉ። ምክንያቱም ቤቱ ሰፋ ያለ ቦታ እንዲኖረው ከማስቻሉም በላይ እነዚህ ሁለት ምሰሶዎቸ ቤቱን በሶስት እኩል ቦታዎች በመክፈል ለአገልግሎት ምቹ ስለሚያደርጉ ነው። የመጀመሪያው ሲሶ አቶ ረዳና ወይዘሮ አዳነች እንግዳ ያስተናግ ዱበታል፡ ምግብ ይበላበታል፡ የእጅ ሥራ ይሠራበታል፣ ለመኝታም ያገለግላል። ዋናው ምድጃም የሚገኝበት በዚህ ክፍል ውስጥ ነው። ባለሶስት ጉልቻ ከሆነው ምድጃ የሚነሳው ጭስ ጥቀርሻ የጠገበውን የሣር ክዳን ጣራ እየሰረገ ወደ ውጭ ይወጣል። የሚቀጥለው የቤቱ ሲሶ ደግሞ ለከምችት የሚያገለግሉ ከጭቃና ከእበት የተሠሩ ቁመታቸው እስከ አምስት ጫማ የሚደርስ ጐታዎች አሉ። ወደ በሩ ያሉት እነዚህ ሁለቱ ሲሶዎቸ በአጠቃላይ «ወለል» ተብለው የሚታወቀው ክፍል ነው። ሶስተኛው ሲሶ ደግሞ ጨለም ያለውና «ማጀት» ተብሎ የሚጠ ራው ነው። ወይዘሮ አዳነች በዚህ ክፍል ነው ምግብና ጠላ የሚያዘጋጁት። ለእንግዶች ከሚዘጋጀው ቡናና ምግብ በስተቀር ቤተሰብቡ የሚበላው ምግብ ብዛቱንም ሆነ ጥራቱን ጎረቤት እንዳያየው ማጀት ውስጥ ነው የሚዘጋጀው።

የቤት እቃዎችንና ቁሳቁሶችን በተመለከተ አልጋ፣ ወንበሮችና በጥልፍልፍ ጠፍር የተሠሩ ሰፋ-መሰል አግዳሚ ወንበሮች የመሳሰሉት ይገኛሉ። እነዚህ እቃዎች በአቶ ረዳና በልጆቻቸው የተሠሩ ናቸው። አንዳንድ ቤቶች ደግሞ ለመኝታና ለመቀመጫ የሚያገለግሉ መደቦች አሏቸው። የእንጨት ሙቀጫ ከነዘነዘናው በያንዳንዱ ቤት የሚገኝ ዕቃ ነው። ወይዘሮ አዳነችና የልጆቻቸው ሚስቶች ጥራጥሬ፣ ለምግብ የሚሆኑ ቅባትና እህል የሚወቅጡበት ሙቀጫና በተጨማሪም የድንጋይ ወፍጮ ተተክሎ ከነመጁ ይገኛል። ዳቦና እንጀራ የሚቀመጥበትና የሚበላበት ሞሶብ እንደክብር የወግ እቃ ይቆጠራል። ሞሰቡ በሸጣጣ ክዳን ተገጥሞ ምግቡ በውስጡ ይቀመጣል። እንዲሁም በጥንቃቄ የተሠራ ምግብ በሞሶብ ሆኖ ይቀርብና እንግዶች ዙሪያውን ከበው ይመገባሉ። አንድም ሆነ ሁለት ከእንጨት የተሠሩ ገበቴዎች በወይዘሮ አዳነችና በልጆቻቸው ሚስቶች የተሰፉ የተለያዩ የስፌት እቃዎች፣ በፊላሻዎች የተሠሩ እንስራዎችና ማሰሮዎች፣ የቅል

ሸክናዎች፣ የልብስ ቁሳቁሶች፣ የእርሻ መሣሪያዎችና የጦር መሣሪያዎች ከሚጠቀሱት የቤት እቃዎችና ቁሳቁሶች መካከል ናቸው::

ከአቶ ረዳ መኖሪያ ቤት አጠገብ ክብ የሆነ ያልተመረገ ቤት የፍየሎች፣ ያህያዎችና በተለይ ደግሞ ገና ያላደጉ እንስሳት የሚጠለሉበት ጋጣ አለ:: ትላልቅ እንስሳት በተለይ ከብቶች፣ ፈረሶችና በቅሎዎች ግን እዚያው አጠገብ በግንዲላና በእሾሃማ አጥር በተሠራው በረት ውስጥ ማታ ማታ ይታጎራሉ:: ዶሮዎች በዋናው ቤት ውስጥ የሚራቡ ሲሆኑ አንዳንድ ቤተሰቦች ደግሞ አህዮቻቸውንና ሌሎች እንስሳትን ሌሊት ሌሊት በቤት ውስጥ እንዲያድሩ ያደርጋሉ:: እያንዳንዱ ቤተሰብ በጭቃና በጨፈቃ የተሠሩ ክብ የሆኑ የእህል ጎተራዎች ከቤቱ ጋር በማያያዝ ይሠራል:: እንዲሁም ከቤት ውጭ የእህል ማከማቻ ክብ ጉድጓድ ይኖራል:: ሚስት ላላገቡ ጎረምሳ ልጆች ለአንድ ሰው መኝታ ብቻ የምትሆን አራት ማዕዘን የሆነች በጭቃና በጨፈቃ የተሰራች ጎጆ (ስቅሉ) ማየት የተለመደ ነው::

የአቶ ረዳ ልጅ መልኬ ድሮ ታላቅ ወንድሞቹ ይኖሩባቸው ከነበሩት ጎጆዎች ቀጥሎ ትንሽ ጎጆ አለችው:: በአቶ ረዳ ቤት ዙሪያ ልዩ ልዩ የጓሮ ተክሎችና ቅመማ-ቅመሞች የሚተከልበት የታጠረ ግቢ (ጓሮ) አለ:: ከዚህም በስተቀር የተለያዩ ሰብሎችና የቅባት እህሎች በሰፊው ታርሰው የሚዘራባቸው የእርሻ ቦታዎች በተለያየ ቦታ ተራርቀው በተቆራረጠ ሁኔታ ይገኛሉ:: በዚህም ምክንያት የአንድ ቤተሰብ እርሻ ይዞታ ኩታ-ገጠም አይደለም:: ሰባ በመቶ የሚሆኑ ያገቡ ወንዶች መኖሪያቸውን ከወላጆቻቸው አጠገብ መመሥረት የተለመደ መሆኑ ቢታወቅም ማንኛውም ትዳር ያለው ጎልማሳ ቢፈልግ ከአማቶቹ አካባቢ፣ ፍላጎትና ምርጫው ከሆነም ከወላጆቹ አጠገብ መኖሪያ ቤቱን ሠርቶ የመኖር ሰፊ ምርጫዎች አሉት::

አንድ ቤት ሠሪ አንዳንድ ጊዜ ቤት ለመሥራት ካቀዳቸው አማራጭ ቦታዎች ላይ ጭብጥ አፈር በመዛገን ወደ ጠንቋይ (አዋቂ) ወስዶ በማሳየት የትኛው ቦታ የተሟላ ጤንነትና ሃብት ሊያስከትል እንደሚችል በማስጠንቆል ቤቱ የሚሠራበትን ቦታ ያስመርጣል:: እስከ 19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ማብቂያ ድረስ ያገቡ ሰዎች «የጢስ ግብር» ለአማራ ሹም ላለመክፈል ሲሉ

ቤታቸውን ከወላጆቻቸው አጠገብ መሥራት የተለመደ ነበር፡፡ የጋራ ቤተሰብ የምንለው አባወራውንና ባለቤቱን፣ ያላገቡ ልጆቻቸውንና እንዲሁም ያገቡ ልጆቻቸውን ከነቤተሰቦቻቸው ያጠቃልላል፡፡ እንደዚህ ያለው ቤተሰብ (ሳቢጠራ) በአንድ ትልቅ ቤት ውስጥ የሚኖሩ ሲሆን ቤቱ ለእያንዳንዱ ቤተሰብ ለመኝታ ቤት፣ ለምግብ ቤት፣ ለማብሰያና ለማከማቻ እንዲያገለግል የተከፋፈለ ነው፡፡ በአሁኑ ጊዜ ግን አዲስ ያገቡ ባልና ሚስት ለትንሽ ዓመታት ከባልየው ቤተሰብ ጋር ከኖሩ በኋላ የራሳቸውን ቤት ሠርተው ጉጆ ይወጣሉ፡፡ በዚህ ዓይነት ሂደት ነጋሽና የሃያ ሰባት ዓመቷ ሚስቱ አልማዝ እንዲሁም አስራ ስምንት ዕድሜ ያላት ፀሐይ ከባለቤቷ ከቢተው ጋር አልፈውበታል፡፡

የቤት ግንባታ ሥራ ሰብል ከተሰበሰበ በኋላ በበጋው ወቅት ተጀምሮ ክረምቱ እስኪገባ ይቀጥላል፡፡ ሥራው በቅርብ የቤተሰብ አባሎች የሚከናወን ሲሆን እቅድ ማውጣትና የጉልበት ሥራው በአቶ ረዳና በልጆቻቸው ይሠራል፡፡ በቅድሚያ የቤት መሥሪያ እቃዎች ይዘጋጁና ቤት ሊሠራ ወደ ተመረጠበት ቦታ ይወሰዳሉ፡፡ ከዚያም ልጆቻቸው ከቁረጧቸው የተለያዩ ዛፎች ለወራጅ፣ ለቋሚና ለምሰሶ ወይም ለወጋግራ የተመረጡት እንጨቶች ተጠርበው ይዘጋጃሉ፡፡ የቤት ሥራው እንደተጀመረ ጉን ለጉን ለማገርና ለግድግዳው የሚያገለግለው ጨፈቃ በየዓይነቱ ተቆርጦ ይቀርባል፡፡ ቀጥሎም ሴቶች ለጭቃና ለእበት ማቡኪያ የሚሆነውን ውሃ እንዳቀረቡ ወንዶች አቡክተው ሴቶች የቤቱን ምርጊት ሥራ እንዲቀጥሉ ያስረክቧቸዋል፡፡ የቤቱ ሥራ ከቤተሰብ አቅም በላይ ሆኖ ባዕድ በሆኑ ሰዎች እንዲሠራ ከተፈለገ፣ አሠሪው መጠጥና ምግብ በቀን አንድ ጊዜም ሆነ ሁለት ጊዜ ማቅረብ ይኖርበታል፡፡ ሁሉም አሁን የማይከተለው ቢሆንም በጥንቱ ልማድ መሠረት አቶ ረዳ ዶሮ አርደው መጠነኛ ግብዣ በማድረግ አዲሱ ቤት ይመረቃል፡፡ በተጨማሪም ከግብዣው ጋር ተያይዞ «መስቂ» የተባለው ልዩ የተባረከ ጠላ ከቤቱ ፊት ለፊት ይረጫል፡፡

## ቅዱስ ቦታዎች

ቅዱስ ቦታዎች (ድግናዎች) ለእያን ዳንዱ የቅማንት ኅብረተሰብ በጣም አስፈላጊና በሕይወታቸው ወሳኝ ጉዳይ ናቸው፡፡ እነዚህ ብዛት ያላቸው ቅዱስ ቦታዎች በአማካይ ደረጃ በሚገኙት ቅማንት ዘንድ ከፍተኛ ግምት የሚሰጣቸው በመሆኑ የቅማንትን ሕብረተሰብ ከሌሎች ጉረቤት ከሆኑ ማኅበረሰቦች ልዩ



አዛውንቱ አባወራ ጠብመንጃ እንግበው ከሚስታቸውና ከልጃቸው ጋር ከቤታቸው አጠገብ የተነሱት። ቤቱ ከድንጋይና ከጭቃ የተሠራ ነው። ብዙ የዚህ ዓይነት ቤቶች በቅማንት አገር አይታዩም።

ያደርጋቸዋል። ቅማንቶች መጸለይ የሚፈልጉት ገላጣ በሆነ ቦታ ላይ ስለሆነ አብዛኛውን ጊዜ የጸሎት ሥነሥርዓታቸውን የማያካሂዱት ሠፊ በሆኑ ድግናዎች ነው። እነዚህ ቅዱስ ቦታዎች ለሁለት ፈጽሞ ለተለያዩ ዓይነት አገልግሎት ይውላሉ። አንደኛው

ለክብረ-በዓል፡ ሌላው ደግሞ ለመቃብር ቦታ በተለይ የተወሰነ ነው:: ድግናዎች ጥንታዊ የባሕል ጀግኖችን ለዘለዓለም ለማስታወስ ታስቦ በእነሱ ስም የተሰየሙ ናቸው::

የክብረ በዓል ሥነሥርዓት የሚካሄደው በዓመት አንድ ጊዜ ለተወሰኑ ዓመት በዓላት ቢሆንም ትማንቶች ዘወትር ስለየዕለቱ ኑሮአቸው መሳካት እክብሮታቸውን ለአምላ ካቸው በድግናዎች ይገልጻሉ:: ለምሳሌ አንድ ግለሰብ ሥራ ጀምሮ እንደሆነ ፍፃሜውን እንዲሠምርለት ይሳላል፡ ወይም እንደሚፈ ጽመው ቃል ኪዳን ይገባል:: እያንዳንዱ ኅብረተሰብ የየራሱ ድግና ሲኖረው ከርከር ሰባት ድግኖች ስሳሏት የመሪነቱን ሥፍራ ይዛለች:: ገሳጣ ቦታ ላይ መጸለዩ ባህላቸው ቢሆንም የጭልጋ ወምበር እየተባለ የሚታወቀው ከፍተኛው የትማንት የሃይማ ኖትና የፖለቲካ መሪ «ሽዋንግ» የሚባል ለተለያየ የጸሎት አገልግሎት የሚውል ቤት አለው:: ይህም የሆነበት ምክንያት ትማንቶች ዙሪያውን ብዛት ባላቸው ክርስቲያኖች በመከበባቸው የሃይማኖት ሥነሥርዓቱን በክፍት ቦታ ማድረግ ባለመፈለጋቸው ነው::

ሌላው በሁለተኛ ደረጃ መንፈሳዊ አምልኮት የሚካሄድበት ቦታ «ቆሌ» ወይም መንፈስ አለበት ተብሎ በሚታወቅ ቦታ ነው:: ይህ ቦታ ድግና ተብሎ ከሚታወቀው የክብረ-በዓል ቦታ በደረጃ ዝቅ ያለ ከአካባቢው መንፈስ (ቆሌ) ጋር ግንኙነት የሚደረግበት ነው ተብሎ ይነገራል:: ቦታው ከትልቅ ተራራ ጫፍ ላይ ወይም የአንድ ገደል አፋፍ ሊሆን ይችላል:: ብዙውን ጊዜ በእንደዚህ ባሉ ቦታዎች ላይ የሚገኝ አንድ ትልቅ ዛፍ ወይም ቋጥኝ ይሆናል::

እነዚህ ቆሌ አለባቸው ተብሎ የሚታመንባቸው አንዳንድ ቦታዎች «ምዝግና» ወይም «አደራ» (እግዚአብሔር) እና ሌሎች አማልእክት የሚታሰቡበት ቦታዎች ናቸው:: አምልኮት ከሚካሄድባቸው ቦታዎች በጣም የታወቀው ጭልጋ ውስጥ ጀልሽብ ከተባለ ቦታ አጠገብ የሚገኘው «አዳሪ ፈርዳዳ» (የእግዚአብሔር ፈረስ) የሚባለው ነው:: በዚህ ኮረብታማ ቦታ ላይ አንዲት ብቸኛ ዛፍ ምልክት ስትሆን፣ አፈ-ታሪካቸው እንደሚያ ስረዳው በጥንት ዘመን እግዚአብሔር ሕዝቡን ለመጐብኘት በፈረስ ወርዶ በነበረ ጊዜ የፈረሱ ኮቴ ያረፈበት ድንጋይ ላይ ምልክቱን ትቶ እንደተመለሰ ነው የሚነገረው:: ሌሎች ቅዱስ የሆኑ ቦታዎች

ደግሞ ምንም ዓይነት የከብረ-በዓል ሥነሥርዓት የማይደረግባቸው ነገር ግን ያለፉት ወንበሮች እስከሬን ያረፉባቸው የመቃብር ቦታዎች ናቸው። የመጨረሻዎቹ ሦስቱ የከርከር ወምበሮች የተቀበሩት አበረክርና በተባለ ቅዱስ ቦታ ላይ ይገኛል።



ከእይታማ ቀሌ ከፍተኛ ቦታ ላይ ሆኖ የሚታየው ከርከር እንቸው ሚካኤል በከፊል ሲታይ፣ በሁለቱ ቁንጮ ተራራዎች መካከል ከእድማስ ባሻገር ጣና ሐይቅ አለ። አካባቢው ወይና ደጋ ነው።

ከርከር ቅማይታይና (የቅማንት መሰብሰቢያ) በተባለ ቦታ አንድ ደልዳላ ተራራ ላይ በወምበር ጃርጊ መቃብር ላይ በጣም ግዙፍ የሆነ የወርካ ዛፍ የሚገኝ ሲሆን ዛፉ የዛሬ 300 ዓመት በሞቱት የቅማንት መሪ መቃብር ላይ ነበር የተተከለው። በአጠገቡ የሰባት ሌሎች ወምበሮች መቃብር በዚሁ ከርብታ ላይ ይገኛሉ። በተለይ የወምበር ጃርጊ መቃበር ላይ ያደገውን ግዙፍ ዋርካ መካን ሴቶች ካዩት መፀነስ እንደሚችሉ ይነገራል። ሆኖም ከቅርቡ ዓመታት ወዲህ በቅማንት ቅዱስ ቦታዎች ላይ ቤተክርስቲያኖች እየታነፁ ናቸው። ለምሳሌ ቅማይታይና በተባለው ቦታ ላይ የከርከር መድኀኒዓለም ቤተክርስቲያን ተተክሎበታል። የአገው የሃይማኖት ቦታዎች ባለፉት መቶ ዓመታት በቤተክርስቲያኖች እየተተኩ መሆኑን በግልጽ የሚያስረዳ መሆኑን እንገነዘባለን።

ከተቀደሱ ቦታዎች ትይዩና መገንጠያዎች ላይ የምናያቸው ለዘመናት የቆዩ ቅቤ የጠጡ የድንጋይ ቁልሎች ሌሎች የአምልኮት መግለጫ ምልክቶች ናቸው። በእነዚህ ቦታዎች የሚያልፉ ቅማንቶችም ሆኑ ወይም ሌሎች ክርስቲያን የሆኑ የቅማንት መንገደኞች ሁሉ አረፍ ብለው ድግናው የተሰየመለትን የባሕል ጀግናቸውን በማስታወስ የሕሊና ጸሎት ያደርጋሉ። በጣም የተለመደው ጸሎታቸው እንዲህ የሚል ነው፡- «በሠላም እዚህ ለመድረስ ያበቃኸኝ ጌታዬ ምስጋና ይድረስህ፡ ወደፊትም ያሰብኩትን ዓላማዬን እንድታሳካልኝ እማፀንሃለሁ» ይላል። ከዚያም መንገደኛው ከያዘው ነገር በትንሹ ቀንሶ ከክምር ድንጋይ ላይ ጥሎ ያልፋል።

# ምዕራፍ አራት

## አረማዊ-ኦሪታዊ ሃይማኖት

ቅማንቶች በአንድ እግዚአብሔር ብቻ ነው የምናምነው የሚሉት። ነገር ግን ሃይማኖታቸው የተለያዩ መለኮታዊ እምነቶች የታከሉበት በመሆኑ አማልእክት ነበሯቸው ለማለት ያስደፍራል። አማልእክቶቻቸው የሰማዩ እግዚአብሔርን፣ ቅዱሳን የባህል ጀግኖችን፣ሌሎች ቅዱሳንንና ቆሌዎችን ያካትታል። ሥይጣን እንዳለም ግንዛቤው አላቸው። ለአማልእክቱ ቀሳውስቱ በሕዝቡ ስም በክብረ በዓል የደም መስዋዕት በማቅረብ ይከበራል።

## ሃይማኖትና ቅማንት

አረማዊ-ኦሪታዊ የቅማንት ሃይማኖት ትኩረትን የሚስብና የዚህ በቅርብ የተሳሰረ ሕብረተሰብ መሠረታዊ እምነት ነው። ይህ ሃይማኖት ቅማንት ማንነቱን አውቆና ጠብቆ ከሌሎች ጉሣዎች ጋር ያለውን ግንኙነት በባሕል አጥር ጋርዶ እርስ በእርሱ ብቻ የተሳሰረ ጉሣ ሆኖ እንዲኖር አድርጉታል። ማንም ቅማንት ያልሆነ ሰው ስለቅማንት ምንነት ቢጠየቅ የሚሰጠው መልስ፣ «ቅማንትን ከሌሎች የኢትዮጵያ ሕዝቦች ልዩ የሚያደርገው ሃይማኖቱ ብቻ ነው»፣ የሚል ነው። ስለዚህም ነው የቅማንትን ባህል ከሃይማኖት ጋር አጣምሮ በትድሚያ መመርመሩ መጠነኛ ጠቀሜታነት ካለው ባሕላዊ፣ ማኅበራዊም ሆነ ኢኮኖሚያዊ አደረጃጀትን ከማጥናት የተሻለ ሆኖ የሚገኘው። ሃይማኖቱ ዕምነትንና መንፈሳዊ ነገሮችን ብቻ የያዘ ሳይሆን በቅማንት ባህል ያሉ ሁሉንም መለኮታዊ (ልዕለ- ፍጡራዊ) ባሕርያት የሚያጠቃልል ነው።

የቅማንትን ሃይማኖት ስንመለከተው ኅብረተሰቡ የሌላ ባህላዊ ተፅዕኖ እንዳይደርስበት እንደመጋረጃ ሆነው የሚከላከሉ የተለያዩ ባሕርያት አሉት። ወደ ኢትዮጵያ የመጡ የውጭ ሀገር ጎብኝዎችም ሆኑ በአካባቢያቸው ያሉት ጉሣዎች ዘወትር እንደሚገልጹት ቅማንቶች የሃይማኖት ሥነሥርዓታቸውን የሚያካሂዱት ከእነሱ ውጭ ማንም እንዳያውቀው በምሥጢር ስለሆነ ከቅማንት በስተቀር ስለሃይማኖታቸው ማንም ዕውቀት እንዲኖረው ስለማይደረግ ሁኔታው ለዓለም «ዝግ» ሆኖ ቆይቷል። የቅማንት ዋናው የፖለቲካና የሃይማኖት መሪ የሆነው «ወንበሩ»፣

በከፍተኛና ዝቅተኛ ደረጃ የሚገኙ ቀሳውስትና በሃይማኖቱ አነስተኛ ተሳትፎ ያላቸው ግለሰቦች በአንድ ላይ ሆነው ነው ጥንታዊ ማህበራዊና ባሕላዊ ደንብና አረማዊ-አሬታዊው ሃይማኖት የራሱ የሆነውን ልዩ ጠባይ ይዞ ለዘመናት እንዲዘልቅ ያደረጉት።

ባለፉት መቶ ዓመታት አማራው የባሕል ለውጥ እንዲደረግ በቅማንቱ ላይ ተፅእኖ ቢያደርግም፣ ሃይማኖታቸው እንደ አጥር ቆሞ ሳያስነካቸው ማንነታቸው ተጠብቆ እንዲኖሩ ረድቶአቸዋል። ነገር ግን በ1880ዎቹ ዓ.ም. አፄ ዮሐንስ አራተኛ ቅማንት ክርስ ትናን ተቀብሎ አማራ እንዲሆን በማስገ ደዳቸው ዋናው የመከላከያ ኪላቸው በመሰበሩ ሃይማኖታቸውና ባሕላቸው እየተመናመነ መጥቶ ብዙዎቹ የአማራን ባህል መቀበል ግድ ሆነባቸው።

ባህል ብዙውን ጊዜ ውስብስብና ከሰው ተፈጥሮ ግንዛቤ ውጭ በሆነ ሁኔታ ከአካባቢው ጋር የሚለማመድ ነው ተብሎ ይታመናል፤ የቅማንት ሃይማኖትንም ስንመለከተው የዚህ መሠረታዊ የሆነ ከአካባቢ ጋር በመለማመድ የሚፈጠር ውርስ ባሕርይ የመነጨ ባህላዊ ውርስ ነው። ሃይማኖት እንደ ቴክኖሎጂ የባህል መለወጥን ማስከተል የሚችል ተፅዕኖ እንዳለው ቢታወቅም፤ የቅማንት ቅድመ-ኢንዱስትሪያል ቴክኖሎጂ የአካባቢያቸውን ተፈጥሮአዊ ክስተቶች በእርግጠኛነት ለመቆጣጠር ካለማስቻሉም በላይ በምን ምክንያት እንደተከሰቱ ለማብራራት ስልቱና ዕውቀቱ ስለሌላቸው ሁሉንም ነገር ለመቆጣጠርም ሆነ ለማስረዳት ከመለኮታዊ ክስተቶች ጋር ያይዙታል።

ቅማንቶች በተፈጥሮ መለዋወጥ ምክንያት ወይም ሌላ ምክ ንያት ሊሰጠው የማይችል ሁኔታ ሲያጋጥማቸው በቀላሉ ተደና ግጠው እጃቸውን አይሰጡም። በአካባቢያቸው ስለአጋጠማቸው ማንኛውም ክስተት እንደ ሁኔታው ሃይማኖታቸው መፍትሄ እንዲያስገኝላቸው ይጠቀሙበታል። በመሠረቱ ከተፈጥሮ ቁጥጥር ውጭ መለኮታዊ (ልዕለ-ፍጡራዊ) የሆነ ክስተት አብዛኛውን ጊዜ ውጤት የለውም ብሎ መናገሩ አስፈላጊ አይሆንም። የታመሙ ሰዎች ይድናሉ፣ ሰብሉ ወቅቱን ጠብቆ ይደርሳል፣ ከብቶች ይረባሉ፣ በአጠቃላይ ማንም ቢሆን ክፋን ከማስታወስ ይልቅ ደግ ደጉን በአእምሮው ይይዛል። ሰብአዊ-ፍጡር አጥንትና ሥጋ የተላበሰ ብቻ ሳይሆን እሱን የሚቆጣጠረው የሚያስብ መንፈስና

አእምሮ ስላለው የሃይማኖት እምነትም እንዲኑን ያድናል ሌላውን ደግሞ ያጠወልጋል:: ዋናው ቁም ነገር ሃይማኖት ጤንነትንና ደህንነትን በመጠበቅ በሕዝቦች መካከል መፋጠጥን በመቀነስ ሰዎች የአእምሮ ጭንቀት ሳያድርባቸው በማኅበረሰብ ተደራ ጅተው ያለጥርጣሬና ፍራቻ እንዲኖሩ ያደርጋል:: ከተፈጥሮ ቁጥጥር ውጭ የሆነውን ክስተት በተመሳሳይ ሁኔታ ጥልቀትና ምጥቀት ላለው መለኮታዊ ኃይል ብንተወው ያልታወቀው እንዲታወቅ ሊያደርግ ይችላል:: ልክ መለኮታዊ «ምክንያቶች» ድርጊቶች «እንዴት» እንደተፈፀሙ መልስ እንደሚሰጡ ሁሉ መለኮታዊ (ልዕለ-ፍጡር) «ምክንያቶችን» መቆጣጠር ማለት «ለምን» ለሚለው ጥያቄ መልስ እንደሚያስገኙ በሰው አምሳል በተፈጠረው በእግዚአ ብሔር የሚያምኑም ሆነ ወይም ሌላ አምልኮ ያላቸው ሰዎች ያምናሉ::

ቅማንቶች ሥጋዊና መንፈሳዊ በሆኑት ዓለማት ውስጥ የሚኖሩ ሲሆን በሁለቱ ዓለማት መካከል ያለውን ልዩነት ያውቃሉ፡ በግልጽ ቅዱሱን ከእርኩሱ መለየት ይችላሉ:: ነገር ግን በቂ የሆኑ ተጨባጭ መረጃዎችን ለማሰባሰብ የሚያስችል ያደገ ቴክኖሎጂ ስለሌላቸው ለየት ያለ ሁኔታ ሲያጋጥማቸው ሁልጊዜ ተግባራዊ በማድረግ ረገድ ይቸግራቸዋል::

## የጥንታዊ አገው ሕዝቦች ሃይማኖት

የደቡብ አረቢያና የእራት ዕምነቶች ከመምጣታቸው በፊት የጥንታዊ አገው ሕዝቦች ሃይማኖት ምን ይመስል እንደነበር ከታሪክና የአገው ትውፊቶች ሠፊ ግንዛቤ ማግኘት ይቻላል:: ኋላቀር በሆነ በዝቅተኛ የግብርና ሥራ ይተዳደሩ የነበሩት ጥንታዊ አገዎች አማልእክት፣ በጣም ሩቅ ነው ተብሎ የሚታሰበውን አንድ «የሰማዩ እግዚአብሔርን»፣ ቆሌዎችን፣ የሰማይ መናፍስትንና የባህል ጀግኖችን ያጠቃልላል:: አንዳንድ ልዩ ዛፎችና እንደ ዘንዶ ያሉ እንስሳት መመለኪያ ነበሩ:: ብቸኛ ዛፎች፣ የተራራ ቁንጮዎችና ወንዞቸ የአማልእክት መኖሪያ ተብለው ስለሚገመቱ የሃይማኖት ሥነሥርዓት ይካሄድ ባቸው ነበር:: አንዳንድ ማስረጃዎች እንደሚጠቁሙት በጥንቱ ዘመን በደንብ የተደራጀ ቀሳውስት አልነበራቸውም:: በምትኩ ግን ከሰማያዊው ዓለም መንፈስ ጋር የአገውን ሕዝብ እናገናኛለን የሚሉ ቃልቻዎች እንደነበሩ እንረዳለን:: ከዚያም ቀስ በቀስ

ሁኔታው ተለውጦ በሕዝቡና በአማልእክቱ መካከል ስለመሬት ልምላሜና ጥሩ ዝናብ ለማግኘት የሚያማልዱ ቀሳውስት ብቅ ማለት ጀመሩ። አንዳንድ ጊዜም ቀሳውስቱ የፖለቲካ አስተዳዳሪነት ስልጣን በተጨማሪ ነበራቸው። ይህም ሲሆን ቃልቻዎች ጭራሹኑ ከሥራቸው ሳይገለሉ ዝቅተኛና ይፋ ያልሆነ ሥነሥርዓት እንዲያከናውኑ ተትተው እስካሁንም በዚሁ መልክ እንደቀጠሉ ይገኛሉ።

ዘገየት ባሉት ዘመናት የሌሎች የሃይማኖት እምነቶች ከአገው ሃይማኖት ጋር በመዳቀላቸው የሃይማኖት መወራረስን ያስከተለ ቢሆንም አብዛኛው የአረማዊ-አገው ሃይማኖት ይዘት ሳይለወጥ ለዘመናት ቆይቷል። ቅማንቶች እንደሌሎች የአገው ዝርያዎች የኦሪትንና የክርስቲያንን መሠረታዊ እምነቶች ሙሉ በሙሉ ባለመቀበላቸው ሃይማኖታቸው በሰሜንና ማዕከላዊ የኢትዮጵያ ደጋማው ክፍል ከሚገኙት ሃይማኖቶች ሁሉ ከፍተኛ የአረማዊ ይዘት ያለው ሊሆን ችሏል።

## የጭልጋን ወምበር ለመጐብኘት የተደረገ ጉዞ

በመጀመሪያው አንዱ የመስክ ጥናት ልምዴ ወንዞች በጉደለበት ወቅት ዋናውን የሃይማኖትና የፖለቲካ መሪ የሆነውን የመጨረሻ የቅማንት ወምበር ለመጐብኘት ወደ ጭልጋ ጉዞ ማድረግ ነበር። ይህም ቅማንትንና ሃይማኖቱን ለማጥናት የመጀመሪያው አስፈላጊ እርምጃ ነበር። ጉዞው ቀላል አልነበረም። ከረዳቴ ከዓለማየሁ ገሠሠ ጋር ወጣ ገባ በሆነው ኮረንኮንች መንገድ ስንጓዝ ቁጥቋጦዎችን መቁረጥ፣ ያሞጠሞጡ ድንጋዮችን ማስወገድ፣ ትናንሽ ኩሬዎችን በድንጋይ መሙላት፣ የተሸረሸሩ ጉድጓዶችንና ጉድቢያዎችን እያስተካከልን መጓዝ ስለነበረብን የጭልጋ አውራጃ ከተማ ወደሆነችው አይከል ለመድረስ ስድስት ሰዓት ፈጀብን። ከተማው ስደርስ ልክ የተፈረደበት የጉዳና ወንበዴ የሆንኩ ነበር የመሰለኝ። የአይከል ከተማ ሕዝብም ሆነ እራሴ ጭምር ያች ትንሽ ቮልስዋገን መኪና ያን ያህል አስቸጋሪ መንገድ አቋርጣ መሃል አገር እንዴት እንደደረሰች ነበር ማመን ያቃተን።



ወምበሩን ማነጋገር መፈለጋችን ገልፀን መልእክት ከላክን በኋላ ድንኳን ተክለን ሠፈርን። ከሁለት ቀን በኋላ መንገዱን የሚያሳየን ሰው ተልኮልን ጉዞአችንን ወደ ወምበሩ መኖሪያ ቤት አቀናን። በመንገዱ ዳር «የእግዚአብሔር ፈረስ» ኮቴ አለበት የተባለውን ድግና መሬያችን አሳየን። ትንሽ እንደተጓዝን የወምበሩ ወንድም በሰላምታ ተቀብሎ ጃልሽብ ወደሚገኘው የወምበሩ ቤት ወሰደን። ሠፈሩ በርካታ ቤቶች ያለበት በባሕር ዛፍና በአገሬው ዛፎች የተከበበ ከመሆኑም በላይ ዙሪያውን እስከ ጉልበት በሚደርስ ጥሬ ካብ ታጥሯል።

ወምበሩ ካሁን በፊት ከብዙ ምዕራባዊያንና ከባህላቸው ጋር ብዙም ግንኙነት የሌላቸውና አንድም የሆሊውድ ፊልም ተመል ከተው የማያውቁ ቢሆንም ለእኔ ያደረጉት ትዕይንታዊ አቀባበል ግን በጣም ካሰብኩት በላይ ነበር የሆነብኝ። ከረዳቴ ጋር ከሠፈሩ ጠርዝ ላይ ወደሚገኘው ወደ አንድ «መሰብሰቢያ» ቤት ተወስደን ስንገባ ሁለት ሦስተኛ የጭቃ ልስን የሆነው ግድግዳ በምሰሶዎች ላይ በተንጠለጠሉ ነጭ መጋረጃ ተሸፍኗል፤ የአፈረ ወለሉ ደግሞ ጥሩ ሽታ ያለው እርጥብ አረንጓዴ የባህር ዛፍ ቅጠል ለብሷል። በቀሪው አንድ ሦስተኛው የግድግዳ ሥር ደግሞ በቀይ ምንጣፍ ያሸበረቀ መደብ አለ። ወምበሩ በሁለት ቄሶች ታጅበው ወንበራቸው ላይ ሲቀመጡ እናትዮዋም ከእግሩ ሥር ተቀመጡ። ቁመናቸው (ከምኞት የተነሣ ሳይሆን አይቀርም) ከሌሎች ሰዎች ረዘም ያሉና ደልዳላ ሰውነት ያላቸው ወምበር መርሻ ሙሉ ነህ፣ ነጭ ልብስ ለብሰው በራሳቸው ላይ ነጭ ጥምጣም አድርገዋል። ከዚህም በላይ በወርቅ የተለበደ ደማቅ ሰማያዊ ካባ ተጎናፅፈዋል። እንደገባን ዝቅ ብለን እጅ ነሣን፤ ነገር ግን ሌሎች ሰዎች እንደተለመደው እንደሚያደረጉት ጉልበት ወይም ጫማ አልሳምንም። እኛ ይህን ብናደርግ ወምበሩን ጨርሶ የሚያረክስ ስለሚሆን አይፈቀድም ነበር።

በተፈቀዱልን ወንበሮች ላይ እንደተ ቀመጥን ለሃይማኖት መሪዎቹ የጉብኝታችንን ዋና ዓላማና ስለምናደርገው የመስክ ጥናት ከማስረዳታችንም በላይ በእኔ በኩል ስለቅማንት ኅብረተሰብና ታሪክ ያለኝን ግንዛቤ ገለፅኩ። ስለኑሮአቸው ያለኝን የማወቅ ፍላጎት ስገልጽ በቦታው ላይ ያሉትን የብዙ ተራ ሰዎችን በጎ አመለካከት ባገኝም ወምበሩ ግን ቁጥብ በሆነ አንደበት በማመንታት እራሳቸውን በመካከት የመስክ ሥራውን እንድቀጥል

ፈቀዱልኝ:: የዚያን ቀንና በሚቀጥለው ቀን ቀጥምር ካደረግነው የረዥም ጊዜ ድርድር በኋላ የወምበሩን መኖሪያ እንድንጎበኝ፣ ደንኳናችንን ካጠገባቸው እንድንተክልና ልዩ ልዩ ሥነሥርዓቶችንም እንድንከታተል ተፈቀደልን:: በቆይታችን ወቅት የተለያዩ ሥነሥርዓቶችን ተከታተልን፣ የተከለከሉና ያልተከለከሉ ባህሎችን በጥንቃቄ ስንዘግብ ሰነበትን:: ከዚህም በስተቀር ስለ ሥነሥርዓቶቻቸው ያለንን በጎ አመለካከት አድናቆት ለሃይማኖት መሪዎችና ሽማግሌዎች በመግለፃችን ከአንዳንዶቹ ጋር የልብ ወዳጅነት ብናተርፍም ወምበሩ ግን ገለልተኛና ግልጽ ያልሆነ አቋም ይዘው ቆዩ::

በመጀመሪያው ቀን ስብሰባችን በተደረገው ውይይት «ሠላብ» (ጠላ) እና «ሚዝ» (ጠጅ) ከመጠጣቱም በላይ ቀሳውስቱ ሕዝቡን በጸሎት መሩ:: የጸሎቱ ሥነሥር ዓትና በእኛና በወምበሩ እንዲሁም በቀሳውስቱ መካከል የሚደረገው ንግግር በቅማንትኛ ቋንቋ ነበር:: ከዚያ በኋላ ለብቻችን ምግብ ተሰጠን:: ሌሎች ግን ቅማንት ካልሆነ እንግዳ ጋር መብላት እንደሚያረክሳቸው ስለሚፈሩ ከእኛ ጋር አልበሉም:: የፀደይ ልምላሜ ጸሎት በተደረገበት ወቅት ከቅማንት መሪዎች ጋር በአንድ ላይ የበላን ቢሆንም የተመገብንበት ሞሰብ ግን ተለይቶ ነበር::

ማኅበራዊ ግንኙነቴን ከወንበሩና ከሌሎች የሃይማኖት መሪዎች ጋር በየጊዜው እያቀራረብኩ በመጣሁ ቁጥር ስለሕልውናቸው መሠረታዊ ጉዳይ ነው ብለው ስለሚቆጥሩት የቅማንት ሃይማኖት ግንዛቤዬ እያደገ መጣ:: ሆኖም ያገኘኋቸውን መረጃዎች ስለትክክለ ኛነታቸው እራሴ ካገኘሁት ግንዛቤ ጋር ማስተያየትና እንዲሁም ከተራ ቅማንቶችና ከሌሎች የጎሣ አባሎች ከምሰበሰበው መረጃ ዎች ጋር ማነፃፀርና ማመሣከር ነበረብኝ::

## ስለዓለም አመለካከትና መሠረታዊ እሴቶች

የቅማንት ሃይማኖት እንደማንኛውም ኅብረተሰብ ሃይማኖት ሁሉ ስለዓለም ያላቸውን አመለካከት ያንፀባርቃል:: የዓለም አመለካከት በባህል በተለይም እንደሃይማኖት፣ አፈ-ታሪክና ልብወለድ በግልጽ የሚታይና የሚነገር ብቻ ሳይሆን ውስጠ-ታዋቂ በመሆኑ፣ በሚገባ ለመረዳት የሚቻለው በባህል ተቋሞች ላይ የሚንፀባረቀውን በመለየትና የሕዝቦችን ባህል አንዱን ከሌላው

ጋር በማገናዘብ በሚደረግ ጥናት የሚገኝ ነው። ትምህርቶች ጥንድ የሆነ ማኅበራዊ አደረጃጀት ስላላቸው በዚህ ሁኔታ ዓለምም በደግና በክፉ ተለይታ በሁለት እንደተከፈለች ያምናሉ። ለእነሱ አረማዊ-አሪታዊ ሕግጋትን መከተል ማለት በገነት ውስጥ ለዘለዓለም በጥሩ ሁኔታ መኖር ማለት እንደሆነ ይገነዘባሉ።



ውምበሩን ለመጉብኘት ወደ ጭልጋ የተደረገው ጉዞ፡ ፎቶግራፉ በበጋው ወቅት ከጃልሽብ አንድ ማይል ወደሰሜን ርቆ ያለውን የመሬት ገጽታ የሚያሳይ ነው።

እስኪተወሰን ደረጃም ቢሆን የአንዳንድ ጐሣ ሃይማኖቶች የኅብረተሰቡ መሠረታዊ እሴቶች ወይም የግብረገብ ሕግጋት ተጠብቀው እንዲቆዩ ይረዳሉ:: በእርግጠኛነት ለማናገር የቅማንት ሃይማኖታዊ እምነቶች ከኅብረተሰቦች የግብረገብ ሕግጋት ጋር የተሳሰሩ ናቸው:: እንደቅማንት ሃይማኖት ያለ እምነት ከኅብረተሰቡ ግብረገብ ሕግ ውጭ የሆነ ነገር ሁሉ በቀጥታ ወዲያውኑ መለኮታዊ የሆነ ውግዘት ሊያስከትል ስለሚችል የኅብረተሰብ እሴቶች ተጠብቀው እንዲቆዩ የማድረግ ኃይል አለው:: ለምሳሌ ከውጭ የሚመጣውን ያልታወቀ መጥፎ ጠባይ እንዳይገባ ያግዳል፡ ከውስጥ ደግሞ አፈንጋጭ ሆኖ የሚነሳውን የተለዬ ጠባይ እንዳይከሰት ይከላከላል:: እንዲሁም ሕብረተሰቡን በቅርብ የሚያስተሳስሩ የሃይማኖት ሥነሥርዓቶች በሚከሄዱበት ወቅት የግለሰቦች ሕልውና እንዲጠበቅ የኅብረተሰቡ ቅዱስነት እየተደ ጋገመ ስለሚሞገስና ስለሚባረክ ይህ ማጠናከሪያና ሙገሳ ኅብረተሰቡ እርስ በእርሱ ተሳስሮ እንዲኖር ረድቷል። ይህን በተመለከተ አንዳንድ ሥነሥርዓቶች እንደአስፈላጊነቱ በዚህ መጽሐፍ ውስጥ አግባብ ባለው አርዕስት ተገልጸዋል::

ቅማንት በተለይ ስለእግዚአብሔርና ስለነፍስ አሬታዊ የሆነ ሥር የሰደደ ጥንታዊ እምነትና አመለካከት አለው:: ሆኖም የአንዳንድ እምነት ሥረ-መሠረት አሬታዊ ላይሆን ይችላል:: ለምሳሌ ያህል ቀዝቃዛና የሚያቃጥለው ሲዖል ከገነት ጋር ስላለው ተቃራኒነት እንደሚከተለው ይገለጻል:: በእምነታቸው «ነፍስ» (ፊዋ) በማንኛውም የሰውነት ክፍል እንደሚኖር፣ ሰው ሲሞት ነፍሱ ወደ ሰማይ እንደሚሄድና በሕይወት ዘመኑ በነበረው ጠባይ መሠረትም ይህች ነፍስ ወደገነት ወይም ወደ ሲዖል እንደም ትወርድ ነው:: ነገር ግን እንደጥን ታዊው የቅማንት ዕምነት ከሆነ ነፍስ ወደ ሰማይ ከሄደች በኋላ ከእግዚአብሔር ጋር እንደምትኖር ነበር:: እንደ ወምበሩ አገላለጽ «ገነት ውስጥ ሰዎች ሥራ አይሠሩም፣ በጥሩ ቤት ይኖራሉ፣ ማር ሞልቷል......» ነገር ግን «ሲዖል ውስጥ ምግብ የለም፣ ሁሉም ቦታ እሳት ያለበትና በጣም ቀዝቃዛ ነው» የሚሉት::

አንድ ቅማንት ወደ ገነት እንዲገባ ከፈለገ የሚከተሉትን ሕግጋት መከተል ይኖርበታል:: (ለመከታተል እንዲረዳ የቅደም ተከተል ቁጥር ተሰጥቷል::) 1ኛ/ አትስረቅ 2ኛ/ የሰውን ሚስት ማማገጥም ሆነ መውሰድ የተከለከለ ነው፣ 3ኛ/ሌሎች ሠይጣናዊ

ሥራዎችን አትሥራ፡ ፬ኛ/ አንድ ሰው በድሎህ ከሆነ ራስህ አትበቀለው እግዚአብሔር እንዲበቀልህ አስማው፡ ፭ኛ/አንዲት ሴት አንድ ባል እንዲኖራትና አንድ ወንድ ደግሞ በአንድ ሚስት እንዲወሰን፡ ፮ኛ/ አንድ ሰው ጥፋት ቢያጠፋ ለባላባታዊ ገዥ ሹም አታሳብቅ፡ የሚሉ ናቸው። የመጀመሪያዎቹ አራት ድንጋጌዎች በቅማንት ኅብረተሰቡ መካከል ግጭት እንዳይኖርና አንድነታቸው እንዲጠበቅ ተግባራዊ የሆኑ ጥንታዊ ሕግጋት ናቸው። አምስተኛው ደግሞ ከክርስትና እምነት የተወሰደና ጥንታዊ ልማዶችን ለማስወገድ የታቀደ ይመስላል። ስድስተኛው ሕግ ደግሞ በየጊዜው እየከበበ የመጣው የአማራ ገዥ መደብ መዋቅር የሕብረተሰባቸውን ድንበር ዘልቆ እንዳይገባ ለመከላከል የተነደፈ ስልት ሳይሆን አይቀርም።

ከቅማንቶች ጋር ባደረግሁት ቆይታ ያካፈሉኝ ምሥጢር ቢኖር አንድ ቀን እግዚአብሔር በፈረስ ሆኖ ይመጣና በመጨረሻው የፍርድ ቀን (ሻምቡሳ) ደግና ክፉዎችን በመለየት ፍርድ እንደሚሰጥ ነው። ጥሩ የሆኑት በጥሩ ጠባያቸው የቅማንት ኅብረተሰብ ባህልን ተጠብቆ እንዲቆይ በማድረጋቸው ውለታቸው ይከፈላቸዋል። በመጨረሻው ፍርድ (ስለተ-ምዕዓት) የባሕል ጀግኖቻቸው በሆነችው በእንተላ የክብረ-በዓል ቀን እንደሚሆን ሲያምኑ ይህም ክርስቲያኖች ከሚያከብሩት የደብረ ዘይት በዓል ጋር ይገጣጠማል። ዓርብ ሌሊት ቅማንቶች በቡድን በመሆን ጸሎት በማድረስ፡ ሰውነታቸውን ታጥበው የነፃ ልብስ በመልበስ ለስለተ-ምዕዓት እራሳቸውን ያዘጋጃሉ። አሁንም ቢሆን ክርስቲያን ቅማንቶች የደብረዘይትን በዓል በክርስቶስ ስም ማክበር ቀጥለዋል። የጭልጋ ቅማንቶችም የልምላሜ ክብረ-በዓላቸውን የሚያከብሩት በዚሁ ዕለት ስለሆነ በቅድመ–ክርስቲያን ዘመን ለዚህ በዓል ምን ያህል ከፍተኛ ትኩረት ይሰጠው እንደነበር ጠቋሚ ነው።

## የቅማንት አማልእክት

የቅማንት ተሳውስት በአንድ አምላክ በእግዚአብሔር እንደሚያምኑ ነው የሚያስረዱት። ነገር ግን ይህ «እግዚአ ብሔር» ከብዙዎቹ ልዕለ-ፍጡራን ሁሉ የበላይ ይሁን እንጂ በዝቅተኛ ደረጃ ሌሎች አማልዕክት እንዳሉ ነው። ምንም እንኳን አንዱ አምላክ የሌሎች አማልእክት የበላይ ሆኖ ቢገኝም በአጠቃላይ ስለቅማንት አማልእክት መነጋገር ተገቢ ይሆናል። ይህ

አመለካከታቸው የመነጨው የአራት ሃይማኖት በቅማንት ሃይማኖት ላይ በአሳደረው ተጽዕኖ ምክንያት ሳይሆን አይቀርም።

«ምዝጋና»፡የሰማዩ እግዚአብሔር። በቅማንት አስተሳሰብ እግዚአብሔር የታው ወንድ ሆኖ መኖሪያው በሰማይ ነው። ከጥ ንታዊ አገው «የሰማዩ እግዚአብሔር» በስውንቱ የተለየ አይደለም፡ እንዲያውም አረታዊ-አረማዊ ፈላሻ አገዎች ከሚያመልኩት የእብራውያን (እስራኤላውያን) እግዚአብሔር ጋር ይመሳሰላል። በጥንታዊው «የሰማዩ እግዚአብሔር» ማመን ጉልህ የሆነ የአረ ማዊነት እምነት ጠባይ ስላለው ቅማንቶችን ከሌሎች ጐረቤቶቹ ከሆኑት ሕዝቦች ልዩ ያደርጋቸዋል። በአንዳንድ አውሮጳውያን ምሁራን ቅማንቶች በፀሐይ እንደሚያመልኩ ቢገለጽም ካደረግሁት የመስክ ጥናት መረጃዎች ትክክል አለመሆኑን ማረጋገጤን ከዚህ ላይ ሳልገልጽ አላልፍም። ቅማንቶች ፊታቸውን ወደምሥራቅ አዙረው የሚጸልዩት እየኖሳሉም በዚህ አቅጣጫ እንደምትገኝ በመገመት እንጂ ፀሐይ በምሥራቅ ስለምትወጣ እሷን ለማምለክ አይደለም።

«የሰማዩን እግዚአብሔር» ቅማንቶች «አደራ» ብለው የሚጠሩት ሲሆን በቋራ የሚገኙ አገውኛ ተናጋሪ ፈላሻዎችም በዚሁ ቃል ነው የሚጠሩት። የቅማንቱ አደራ ስሙ «ምዝጋና» ሲሆን የፈላሻዎች «አደራ» ደግሞ ቢያንስ በሁለት ስሞች ማለትም «ኤሎሂ» እና «አዶናይ» በመባል ይታወቃል። ቅማንቶች ምዝጋና በየትም ቦታ ያለ፡ ፍፁም ኃያል፡ ከእሱ የተሰወረ ምንም ነገር በዓለም እንደሌለና ሁሉም ነገር በእርሱ የተፈጠረ እንደመሆኑ ሁሉንም መልሶ እንደገና እንዳልነበረ የማድረግ ኃይልና ሥልጣን እንዳለው ያምናሉ። እግዚአብሔር ሰውን በራሱ አምሳል የፈጠረ ስለሆነ ቅማንቶች «ምዝጋና» ሰውን ይመስላል ይላሉ።

የቅማንት ቀሳውስት አልፎ አልፎ ከምዝገና ጋር በቀጥታ ይገናኛሉ ቢባልም አብዛኛውን ጊዜ ግንኙነታቸው ቅዱሳን በሆኑ የባሕል ጀግኖቻቸው አማካይነት ነው። «ቅዱስ» የሚለው ስያሜ «ለመላእክት» እና «ለተቀደሱ» ወይም «ለተባረኩ» ሰዎች ወይም ቦታዎች የሚሰጥ ነው።ይህም ማለት የሞቱ ሰብአዊ-ፍጡር የሆኑ የባህል ጀግኖችን፡ መናፍስትንና መላእክትን የሚመለከት ነው። አንዳንዶቹ በእነዚህ በሁለቱ ምድቦች የሚገኙት ፍጥረታት

ምናልባት በዝቅተኛ ደረጃ የነበሩ አማልእክት (ምልኪ) ሳይሆኑ አልቀሩም።

የባሕል ጂግኖች (ምልኪ)። በቅማንት አገር ማንኛውም የባህል ጂግና በስሙ የሚጠራ የተቀደሰ ድግና (ደን) አለው። የእያንዳንዱ ጂግና ክብረ-በዓል የሚውልበት ቀን የታወቀ ስለሚሆን በዓመት አንድ ጊዜ በድግናው በሚደረግ ታላቅ ክብረ-በዓል ጥንታዊው የባሕል ጂግና ታስቦ ይውላል። በዚሁ እለት የተሰበ ሰበውን ሕዝብ ከምዝግና ጋር እንደሚያማልድ ይገመታል። የአገው፣ የአማራና የትግሬ ኅብረተሰቦችም ቢሆኑ እግዚአብሔር ይቅር እንዲላቸው የሚያማልዷቸው አንዳንድ ኃያል የሆኑ መላእክት አሏቸው። (እዚህ ላይ ሳይጠቀስ የማይታለፈው በሥጋዊ ዓለም ቢሆን ኅብረተሰቡ ወደ ከፍተኛ ባለሥልጣኖች አማላጅ በመላክ ለችግሩ መፍትሄ እንደሚሻ የተለመደ ባህል መሆኑ ነው።) የቅማንት የባህል ጂግኖች የእነዚህን ጂግኖች ጥንታዊ አባቶችንና የአንዳንዶችን ሚስቶችም ይጨምራል።

የባህል ጂግኖች በድግናቸው ዘለዓለማዊ ኗሪ ናቸው ተብሎ ስለሚገመት ቅማንቶች በሃይማኖታቸው ምክንያት በጠበቀ ሁኔታ በቃል ኪዳን ተሳስረው እንዲኖሩ አድር ጓቸዋል፤ እንዲያውም ይህ ሁኔታ ከሌሎች ጐረቤት ኅብረተሰቦች ጋር ሲመዛዘን ምንም ተወዳዳሪ የሌለው መሆኑን እንገነዘባለን። ለእነሱ ድግናዎች በዚህ ዓለምና በገነት ከሚኖረው «ምዝግና» ጋር የሚያገናኙ ቀጥታ መስመሮች ናቸው። ቅማንቶች እንደሚ ያምኑት ቅዱሣን ሰዎች ከልባቸው ለምዝግና ጥልቅ ጸሎት ካደረጉ ከእርሱ ጋር መገናኘት እንደሚችሉና ከዚህ ዓለም እንደሚሰወሩ ይናገራሉ። ይህንን ሁኔታ ለማስረዳት የሚሞክሩ ብዙ አፈ-ታሪኮች አሉ። የባሕል ጂግኖች ድግና ከገነት ጋር ግንኙነት ያላቸው ከመሆኑም በላይ ማንኛውም ቅማንት ምዝግና እጅግ በጣም በቅርብ እንዳለና ሃይማኖቱም በጥልቅ ስሜት መመለክ እንዳለበት ያምናል።

የጥንት ተረቶች (ምልኪ) ባህል ገላጭና ተጨባጭ ሁኔታዎችንና ተፈጥሮአዊ ክስተቶችንም ለማስረዳት የሚሞክሩ የተቀደሱ አፈ-ታሪኮች ናቸው። የቅማንት አፈ-ታሪኮች ሕዝቡን ካለፈው ጥንታዊ ዘመንና ከመጀመሪያው የቅማንት አገር ሠፋሪ የባሕል ጂግና ትውልድ ጋር የመገናኛ መስመሮች ናቸው። ይህም

እስከአሁን የመሬት የደገባኛል ጥያቄ ለሚያቀርቡት ደጋፊ ማስረጃ ሆኖ እየቀረበ ነው፡፡ ለምሳሌ የጭልጋው ወምበር አሥራ አራት ትውልድ ወደኋላ በመቁጠር እስከ ትውልዱ የባህል ጀግና ይደርሳል፡፡ እነዚህ የጥንት ተረቶች ለኅብረተሰቡ አንድነትና ጥበቃ አስፈላጊ የሆነውን ሃይማኖታዊ ግብረገብነት የሚያጠናክሩ ናቸው፡፡

የቅማንት አፈ-ታሪክ ጥንታዊና የመጀመሪያው የባህል ጀግና ከሆነው ከአይነር (ያነር) ይጀምራል፡፡ ስለአይነር ብዙ ስለማይ ታወቅ ብዙ አፈ-ታሪክ አወቂዎች የእሱ ልጅ የሆነውን አይደርኪን ይተካሉ፡፡ እንደ ልጁ አይደርኪና እንደ የልጅ ልጁ ክብርዋ፣ አይነር «የመጀመሪያው ቅማንት በኢትዮጵያ» ተብሎ ይታወቃል፡፡ አንዳንድ መረጃ ሰጭዎች የእብራውያንን የዘር ሐረግ በመምዘዝ አይነር የከንዓን የልጅ ልጅ የኖህ ልጅ የሆነው የካም አራተኛው ልጅ መሆኑን ይገልጻሉ፡፡ እንደ አንዳንዶቹ አፈታሪክ ደግሞ የከንዓን ልጅ አርዋዲ ወደ ኢትዮጵያ እንደመጣ የሚያስረዱ ሲሆን ሌሎች አፈ-ታሪኮች ደግሞ የአርዋዲ ልጅ አይነር ነው በመጀመሪያ የመጣው ይላሉ፡፡ ነገር ግን የአይነር ሚስት አንተላ እየተባለች ትጠራ እንደነበር ሁሉም ይተማመናሉ፣ ይስማማሉ፡፡ (ቁጥር አንድ ቻርትን ይመልከቱ)፡፡

እንደ አፈ-ታሪካቸው በሰባቱ የድርቅ ዘመን (ከሰባት ዓመቱ በመጽሐፍ ቅዱስ ከተጠቀሰው የረሃብ ዘመን ጋር ለማገናኘት ሊሆን ይችላል) የአይነርና የአንተላ ልጅ አይደርኪ ዝናብ እንዲዘንብ ሕዝቡ ተራራ ላይ ተሰብስቦ ወደ ምዝግና እንዲጸልዩ ይነግራል፡፡ ጸሎታ ቸውን ጨርሰው ወደቤታቸው ከመድረሳቸው በፊት ዝናብ ይጥልና ከሰባት ዓመት በፊት የተዘራው እህል በቅሎ ለምርት ደረሰ ይባላል፡፡ በዚህ መልክ የቅማንት ቀሳውስት ዝናብ እንዲጥል ጸሎት ያደርጋሉ፡፡ ቅማንቶች የድርቁን አፈ-ታሪክ ደጋግሞ በመናገር ሃይማኖታቸው ፍቱን እንደሆነ የሚያስገነዝቡ ሲሆን፣ ይህም ሁኔታ በእያንዳንዱ የቅማንት አእምሮ ውስጥ እንደሠረፀ ነው፡፡ የአይደርኪን ባለቤት አንዞኮናን አንዳንድ ጊዜ ከቅድስት ድንግል ማርያም ጋር ያመሳስሏታል፡፡ ይህም በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ከክርስቲያን ዕምነት ጋር በመመሳሰል ሃይማኖትን ለማስታረቅ ታስቦ የተደረገ ሳይሆን አይቀርም፡፡

ቅማንቶች አጠር በአለና በተጠቃለለ መልክ ስለታሪካቸው ከጥንታዊ አፈ-ታሪኮች ግንዛቤ በማግኘታቸው በሌሎች ሕዝቦች አኳያ በየትኛው ቦታ ላይ እንደሚገኙ እንዲያውቁ ረድቷቸዋል። ለምሳሌ ያህል ሁሉም የአገው ቅርንጫፎች ተብለው የሚቆጠሩት በጉግ የተዛመዱ ለመሆኑ ከቅድመ አያቶቻቸው ከአይደርኪ ልጆች ጥንታዊ ታሪክ ለመረዳት ይቻላል። ይኸውም አይደርኪና እንዛኩና ሰባት ልጆች የነበሯቸው ሲሆን ሦስቱ ላስታ ወደተባለ የአገው ክልል፣ ሁለቱ ጉጃም ውስጥ ወደሚገኘው አገው ምድር፣ ሁለቱ ደግሞ አሁን ክርከር እየተባለ ወደሚጠራው አገር እንደሄዱ ነው የሚነገረው። አንዳንድ የቅማንት ዘር ቆጣሪዎች የአገው ባህል ከአንድ ሚስት በላይ ይፈቅድ ስለነበር አይደርኪ ሁለት ሌሎች ሚስቶች እንደነበሩት ይናገራሉ። የመጀመሪያዋ ስሜንዳራ የምት ባለው የስሜን አገዎች እናት፣ ሌላዋ ደግሞ ፈያንባሁራ (የፈላሻ ልጅ) የተባለችው የፈላሻዎች እናት እንደነበረች ይጠቁማል።

ካዲስቴ እና ክብርዋ አሁን ክርከር እየተባለ በሚጠራው ቦታ የሠፈሩት የአይደርኪና እንዛኩና ወንድ ልጆች ናቸው። ካዲስቴ ልጅ ያልወለደ ሲሆን በእሱ ስም የሚታወቁ ድግናዎች በክርከር፣ በሜንጨቅና በጋሻ-ጋላገር ይገኛሉ። ከሁሉም በላይ ከፍተኛ ደረጃ የሚሰጠው ክብርዋ የተባለው የባህል ጀግና ነው «ክብር» እየተባለ የሚሰጠው መጠሪያ ከዚህ ዘር ጋር በአባት ሐረግ ግንኙነት ያለው ነው። ክብርዋ በደቡብ ክርከር ሜፍ በሚገኝ በስሙ በሚጠራው ድግና (ደን) አካባቢ ይኖር እንደነበረ ይነገራል። የጭልጋው ወምበር በዚህ ድግና በመገኘት የሥልጣን ብቃቱ በክርከር ወምበር ይረጋገጥለት ነበር። ክብርዋ እንደቅዱሳን የሚከበሩ ዘጠኝ ልጆች ነበሩት። እንደ አፈ-ታሪካቸው ጋድሁና ባዙ የተባሉት ሁለት ልጆቹ በጊዜው ከነበረው ከፈላሻ አገው ንጉሥ ጋር በተደረገ ስምምነት መሠረት ከጥዋት ጀምሮ እስከ ፀሐይ ግባት በፈረስ ጋልበው የሚያቋርጡትን አገር ሁሉ እንዲይዙ ፈቅዶላቸው ሳለ ጋድሁ ፀሐይ እንዳትጠልቅ ለሦስት ቀን አግቶ በማቆየቱ ሠፊ ተጨማሪ መሬት ለመያዝ እንደቻለ ይነገራል። ይህ አፈ-ታሪክ በአንድ በኩል የቅማንትን የመሬት ይዞታ ያጠናክራል፣ በሌላ በኩል ደግሞ በጥንት ዘመን ኃይለኛ ከነበረው ከፈላሻ ጋር በጥላቻ መንፈስ ይተያዩ እንደነበረ የሚያንፀባርቅ ነው።

መላእክት:: ቅዱስ የሚለውን ቃል ለባህል ጀግኖች ብቻ አልነበረም የሚጠቀሙበት:: ከኦሪታውያንና ከክርስቲያኖች መላእክት ጋር ለሚያመሳስሏቸው አማልዕክትና ሌሎች ልዕለ ፍጡራንም ይጠቀሙበታል:: ምናልባት በጥንቱ ዘመን እንደ ስማይ መናፍስትና ዝቅተኛ አማልዕክት ይታዩ የነበሩት ሊሆኑ ይችላሉ:: ቅዱስ ጂጋራንቲ፣ ቅዱስ ሚካኤል እንደሆኑና ቅዱስ ገርጂሊዋሊ እና ቅዱስ ገብርኡ ግን ከሌሎች የኦሪትና ክርስቲያን መላእክት ጋር የሚመሳሰሉ አይደሉም:: ምናልባት ቅዱስ ገብርኤል ብቻ ነው ከኦሪትና ከክርስቲያን እምነቶች ስሙ እንዳለ የተወሰደው መልአክ፡ ምክንያቱም ሌላ የቅማንት ስም የለውም:: እንዲያውም ቅማንት ስለመላእክት ያላቸውን ግንዛቤ ያገኙት ሁሉም አገዎች የኦሪት ሃይማኖት በተቀበሉበት ጊዜ ማይሆን አይቀርም:: በአጭሩ ስለመላእክት ያላቸው አመለካከት ኦሪታዊ መሆኑን ነው የምንገነዘበው::

ሌሎች ቅዱሳን:: የቅማንት ሃይማኖት በመጽሐፍ ቅዱስ የተጠቀሱ የዕብራዊ ሰዎችን ስም ያነሳል:: ብዙ ጊዜ ሰዎች ሲመርቁ «ቤታችሁ እንደአብርሃም ቤት ይሁን፡ እንደአ ብርሃም ሀብቱን ይስጣችሁ» ይላሉ:: እንዲሁም አዳም የመጀመሪያው በምዝግና (እግዚአብሔር) የተፈጠረው ሰውና የሕዝቦቹ ሁሉ ምንጭ እሱ ነው ብለው ያምናሉ:: ሙሴን «በታቦተ-ሙሴ መዝሙር» ላይ ብቻ ነው ስሙን የሚያነሱት:: ይህም በብዙ ክብረ-በዓል ሥነሥርዓቶች ይዘመራል:: ነገር ግን ከፊል ኦሪታዊ በሆነው ጥንታዊ አፈ-ታሪካቸው አይደርኪ በአጋጣመው አንድ ጭቅጭቅ ላይ ሙሴን ለምስክርነት ጠርቶት በሀሰት ስለመሰከረ አይደርኪ በመቆጣቱ ሙሴን ከምድረ ገጽ እንዲጠፋ አድርጎታል ይባላል:: አሁንም ቅማንቶች ዕውነቱን ደብቆ በውሸት የሚመሰክረውን ሰው «ሙሲ» ብለው ይሰድቡታል:: የእስኮትላንድ ተወላጅ የሆነው አገር ጎብኝ ጀምስ ብሩስ ቅማንቶች የዮናስ ዘር ነን ብለው ስለሚያምኑ ዓሣ ከመብላት ይቆጠባሉ ብሎ ዘግቧል:: ሆኖም ይህ በተጨባጭ ማስረጃ ያልተደገፈ አባባል እንጂ እውነተኛው ቁምነገር ቅማንቶች ዓሣ የማይበሉበት ምክንያት ሁሉም የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪዎች ዓሣ መብላት በባህላቸው የተከለ ከለ በመሆኑ ነው:: በመሠረቱ ቅማንቶች ዮናስን አያውቁትም::

የአካባቢ ቆሌ(መናፍስት ):: በቅማንቶች ዘንድ በተፈጥሮ በዓይን ከሚታዩት ሰውና እንስሳት በተጨማሪ ሌሎች የማይታዩ

ረቂቅ ልዕለ-ፍጡራን «ቆሌ»(መናፍስት) ተብለው የሚታወቁ አሉ። ቆሌዎች በአካባቢያቸው ባለው መኖሪያቸው የተወሰኑና በአንድ ሠፈር በሚኖረው ሕብረተሰብ ብቻ የሚታወቁ በዝቅተኛ ደረጃ ያሉ መናፍስት ናቸው። መጠሪያቸውም በሚገኙበት የቦታ ስያሜ ነው። ለምሣሌ የጊጃን ቆሌና የአይንባ ተብለው በሚኖሩበት ሠፈር የሚጠሩ ቆሌዎች አሉ።



ቁጥር 1 ቻርት፣ የከብር የዘር ሐረግ፣ ከባሕል ጀግኖች ጋር ያላቸው ግንኙነትና ከሌሎች ቅማንቶችና ከአገዎች ጋር ስላለው ግንኙነት መግለጫ።

ቆሌ የሚባለውን መንፈስ የግለሰቦች ተያዥና ሞግዚት አያልን የምንጠቀምበት ስያሜ ስለሆነ ወደፊት ሰፋ ባለ መልክ እናየዋለን። ይህ የአካባቢ ቆሌ የምንለው በጥንታዊ የቅማንትና የኩንፈል አገው ሃይማኖት ውስጥ የነበረ ትውፊት ነው። የአዊያና የፈላሻ አገዎችም በመጠኑም ቢሆን ያመልኩታል። እንዲሁም በቤተክርስቲያን የተወገዘና ያልተፈቀደ ቢሆንም በርካታ የአማራ ኅብረተሰቦች (አንዳንድ ቄሶችን ጨምሮ) የአካባቢያቸውን ቆሌ ከልብ ያከብራሉ።

በኅብረተሰቡ ላይ ሊመጣ የሚችለውን አደጋ ለመከላከል፣ ግጭትና በሽታ እንዲወገዱ፣ እንዲሁም የተስተካከለ ዝናብ እንዲዘንብ ቆሌውን በሥነሥርዓት ከተለማመኑ ችግሮች ይፈታሉ ብለው ያምናሉ። ለምሳሌ ከርከር ውስጥ የሚገኘው የአይንባ ቆሌ በአንድ ተራራ ጫፍ ላይ በሚገኝ አንድ ብቸኛ ዛፍ ይኖራል ስለሚባል በተለይ የተሟላ ዝናብ እንዲያስገኝላቸው የእርሻው ወራት በሚጀመርበት ወቅት ይለማመኑታል። የጊጃን ቆሌ ተብሎ የሚታወቀው ደግሞ ከዚያ ቦታ ትንሽ አለፍ ብሎ በስተምዕራብ በኩል ከርከርን አቋርጦ በሚያልፍ ተረተር ጫፍ ላይ ይገኛል ነው የሚባለው። ይህን ቆሌ የመኸር ወቅት ሲደርስ ዝናቡ እንዲቀንስ ወይም እንዲያቆም ይለማመኑታል። ቆሌዎችን በመማፀኑ ሥነሥርዓት ላይ ሁሉም የኅብረተሰብ ክፍል በተገኘበት በሕዝቡ መዋጮ የተገዛ ነጭ በሬ ወይም በግ ለመስዋዕት ይቀርባል። በሬው ወይም በጉ በቅማንቱ ቄስ ይታረድና ደሙን ቆሌዎች እንዲጠጡት ይተዋል፣ ሥጋውን ጥሬውንም ሆነ ቀቅለው ቄሶች ከበሉት በኋላ የተረፈውን መሬት ውስጥ ቀብረው ይሄዳሉ። ይህ የቆሌ መኖሪያ ከባህል ጀግኖች ድግና ጋር ግንኙነት የለውም።

የአሪት ሃይማኖት ከቅማንት አረማዊ ሃይማኖት ጋር ከመዋሃዱ በፊት ለቆሌዎችና ለሰማዩ መናፍስት ከምዝግና ይልቅ የበለጠ እለታዊ የሃይማኖት ሥነሥርዓቶች በስማቸው ይካሄድላቸው ነበር። አሁንም ቢሆን ምዝግና የአማልእክቱ የበላይ ይሁን እንጅ እነዚህ መናፍስት የሚፈለጉና በየእለቱ የሚታወሱ ናቸው።

# ሠይጣን

ሠይጣን የሚለው ስያሜ ከአረት እምነት የተወሰደና በሁሉም አገሮች ዘንድ የታወቀ ልዕለ-ፍጡር ነው። በኢትዮጵያዊያን «ጋኔል» ተብሎ ሲሰየም «ሠይጣን-ጋኔል» ብሎ በአንድ ላይ እያደነ መጥራት የተለመደ በመሆኑ ይህ ሁኔታ የእብራውያንና (አረት) የአገው እምነቶች መደባለቃቸውን የሚያስረዳ አንድ ምሳሌ ነው። ሠይጣን ክፉ የሆነ ነገር ሁሉ የሚመሰልበት ነው። በቅማንት፣ በአማራና በፈላሻዎች አስተሳሰብ ሠይጣን በጣም ጥቁር የሆነ አስፈሪ መልክ ያለው፣ በሰውም ሆነ በእንስሳት አካል የሚመስል እንደነጎድጓድና መብረቅ ያለ ከፍተኛ ኃይል ማምጣት የሚችል ልዕለ-ፍጡር ነው።

አንድ ሰው ከሠይጣን ጋር በመወዳጀት ክፉ ለመሥራት ሥልጣን ሊያገኝ ይችላል። እንዲህ ዓይነቱ ሰው ጋኔል ሳቢ ተብሎ ይጠራል። ከዚህም በስተቀር ክብ በሆነው የኢትዮጵያ ቤተክርስቲያን በውጭ ባሉት ሦስት ግድግዳዎች መጋጠሚያ ላይ በመፀዳዳትና ሽንት በመሽናት ግለሰቦች ጋኔል መሳብ እንደሚችሉ ይነገራል። በዶክተር ፎስተስ የልብወለድ መፅሐፍ እንደተገለፀው ጋኔል ሳቢ ይህን ሠይጣናዊ ሥልጣን የሚያገኘው ዘለዓለማዊ የሆነችውን ነፍሱን ሽጦ ነው። አንድ ጋኔል ሳቢ ግለሰብ ሰውን ሊገድል፣ የሰዎችን ቤት በርቀት ሊያጥል፣ በሠይጣን እየተመከረ ሰውን ሊፈውስ፣ እንዲሁም ለአንዱ ድኅነትን ለሌላው ሀብትን ሊያመጣ ይችላል። የጋኔል ሳቢን አገልግሎት በገንዘብም ሆነ ሌላ እቃ በመስጠት ማግኘት የተለመደ ነው። ብዙ ሰዎች እንደሚያምኑት እነደቆሌዎች ጋኔልና ጋኔል ሳቢዎች በተራራ ጫፍና በወንዞች አካባቢ እንደሚኖሩ ነው። ይህ ዓይነቱ እምነት ስለሠይጣን ያለው የአሪታዊያን ዕምነትና ስለ ቆሌ ያለው የአገው እምነት እንዴት እንደተወራረሱ የሚጠቁም ነው።

ብዙ ጊዜ ደግሞ ከመጻሕፍት አንዳንድ ጥቅሶችን በመድገም የሠይጣንን ድጋፍ መጠየቅ እንደሚቻል ይነገራል። አብዛኛው የኢትዮጵያ ሕዝብ ያልተማረ በመሆኑ የክርስቲያን፣ የፈላሻና የእስላም ቀሳውስት አንዳንድ ጊዜ ጋኔል ይጎትታሉ ይሏቸዋል። እስከቅርብ ጊዜ ድረስ የሃይማኖት መጻሕፍት ያሉ ሲሆን የክርስቲያኖችና የፈላሻዎች በኢትዮጵያ ጥንታዊ ቋንቋ በሆነው በግዕዝ፣ የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች ደግሞ በጥንታዊ

አረብኛ ቋንቋ የተጻፉ ናቸው:: እነዚህ በብራና ላይ በእጅ የተጻፉ መጻሕፍት ቅዱስ ናቸው ተብለው ስለሚታመኑ ያልተማረው ክፍል በውስጣቸው የያዙትን ቁምነገር ስለማያውቅ በፍርሃት ስለሚመለ ከታቸው የተማረው ክፍል ባልተማረው ገጠሬ ላይ ... ሥልጣን መግሪያ ሲያደርጋቸው ቆይቷል::

## ቀሳውስት

ወምበሮች: ወምበሩ የቅማንት የሃይማኖትና የፖለቲካ መሪ ነው:: በዚህ መልክ ሁለት ሥልጣን አጣምሮ መያዙ በሌሎች ጉማዎች ያልተለመደ በመሆኑ ቅማንትን በሰሜናዊው ማዕከላዊ ኢትዮጵያ ካሉት ሌሎች ጉማዎች በጣም ልዩና ብቸኛ ያደርገዋል:: ስለወምበሮችና ስለሌሎች ቀሳውስት በፖለቲካው ረገድ ስላላቸው ሚና በዚህ መጽሐፍ በምዕራፍ ስድስት ላይ ይታያል:: ከዚህ ላይ ሳይጠቀስ የማይታለፈው ግን ቀሳውስት በሥልጣን ተዋረድ በሚገባ የተደራጁና በሰዎችና በሰማያዊው ዓለም ካሉት አካላት ጋር ግንኙነት ማድረግ የሚያስችላቸውን ተገቢ የሆኑትን መደበኛ የአመራር ሥርዓቶች መማርና ማወቅ እንዳለባቸው ነው::

ወምበሩ በግብረ-ገብ የታነጸ፣ የፍጹምነት ምሳሌ የሆነና የኀብረተሰቡ ምድራዊ መልካም ጠባይ የበላይ ጠባቂ እንደመሆኑ በግልጽ ቅማንትነትን ያንፀባርቃል:: በዋና ዋና ክብረ-በዓላት ሥነሥርዓት በመሪነት በመገኘት ተፈጥሮ ያላትን ፀጋ እንድት ለግሳቸው በሚያደርጉት ሥርዓተ-ቅዳሴዎች ላይ ይገኛል:: የተስተ ካከለ የአየር ጠባይ እንዲኖር፣ በሽታና አንዳንድ የግል መጥፎ እድል እንዳያጋጥም፣ አደገኛ አውሬዎች እንዲጠፉና ሕገ-ወጦች እንዲቀጡ ወንበሩ በመጸለይ የቅማንት ሕዝብ የማያስጋና የተረጋጋ ኑሮ እንዲኖር ያደርጋል:: ዋና ሥራው ደግሞ አንድ ሰው ሲሞት ከቀብሩ በፊት ሟች ወደ ገነት እንዲገባ እንዲያስችለው የሚመራቸው ሥርዓተ-ጸሎቶቸ ናቸው::

በተጨማሪም ወምበሩ በሰዎችም ዘንድ ሆነ በተፈጥሮ ልምላሜ እንዲኖር ይጸልያል:: በአፀፋው አንዲት መካን የሆነች ሴት ለሚደረግላት ጸሎት ስጦታ ትሰጣለች:: ወምበሩ በዓመት አንድ ጊዜ በሚኖረው ዋናው ክብረ-በዓል በፀደይ ወራት የሚደረገው የልምላሜ ሥርዓተ-ጸሎት ነው:: በዚህ በዓል ወምበሩ

መስዋእት አያቀርብም። እንዲያውም ቢላዋም ሆነ የጦር መሣሪያ በእጁ መያዝ ስለማይፈቀድ ምግቡ እንኳን ሳይቀር ተቆራርጦ ነው የሚሰጠው። በነገራችን ላይ ሁለት የከፍተኛ ወምበሮች መደቦች ነበሩ። አንዱ በከርከር የሚገኘው ሲሆን ከ1950ዎቹ ዓ.ም. አጋማሽ ጀምሮ ወምበር አልተመደበበትም። ሌላው ደግሞ ጭልጋ የሚገኘው ወምበር ነው። ጥንት በከርከርና በጭልጋ ወምበሮች ሥር አነስተኛ ሥልጣን የነበራቸው ንዑስ ወምበሮች የነበሩ መሆኑ ቢታወቅም በ1880ዎቹ ዓ.ም. ቅማንቶች በክርስትና ሃይማኖት በመጠመቅ የአማራን ባህል እንዲቀበሉ ማድረግ ከተጀመረበት ጊዜ ጀምሮ እየከሰሙ መጥተዋል።

አንድ ወምበር ሲያረጅ ወይም ሲሞት የቅማንት ወንዶች ከ«የታንቲ» የዘር አብራክ ክፍል ከተሻለውና የበለጠ ክብር ካለው ከ«ክብር» የዘር አብራክ ክፋይ ተተኪውን ይመርጣሉ። የጭልጋ ወምበር የቄስ ሐረግ ካላቸው ከባዙ፣ ከጋድሁና ከሸማናሁ ትውልድ ምርጫ ተካሂዶ አንዱ የሚሾም ሲሆን የከርከርም ወምበር በዚሁ ዓይነት ሥነሥርዓት የቄስ ሐረግ ካላቸው ከናዚ፣ ከየንጋሲና ከየዛና ትውልድ ይመረጣል።

በዳግማዊ አፄ ምኒሊክ ዘመነ መንግሥት (እ.ኤ.አ. 1889-1913 ዓ.ም.) አስረሳ የተባሉት ለመጨረሻ ጊዜ በምርጫ የተሾሙት የከርከር ወምበር በ56 ዓመት ዕድሜያቸው ነበር። ወምበር አስረሳ በአባት የዘር ሐረግ የናዚ ዘር ነበሩ። እሳቸውን የተኩት ወምበር ጉሹ የተባሉ የያንጋሲ የአባት ጐሣ ዘርፍ ተተክተው በቦታው ላይ ቆይተዋል። እ.ኤ.አ. በ1915 ዓ.ም. አካባቢ የአስረሳ ልጅ ጉንጥ በ45 ዓመታቸው በምርጫ ሳይሆን በሕዝብ ጠቅላላ ስምምነት ወምበር ሆኑ። በዚያን ጊዜ ግማሽ የሚሆነው የቅማንት ሕዝብ ክርስትናን ተቀብሎ ነበር። የወምበሮች ሥልጣን በአለመግባባትና በረብሻ ምክንያት አደጋ ላይ በመውደቁና ወምበሮች ጥንት ያገኙ የነበረው ጥቅማጥቅም እየተመናመነ በመምጣቱ ከሦስቱ የታወቁ ዘሮች የነበሩት ወንዶች ለኃላፊነቱ ብዙም አልጓጉለትም ነበር። ቀደም ብሎ «ከመዘና» (ከፍተኛ ቄስ) የነበሩት ወምበር ጉንጥ ማንንም ሳይተኩ እ.ኢ.አ. በ1955 ጉንደር ከተማ ውስጥ ሞቱ።

ስለመጨረሻዎቹ ስምንት የጭልጋ ወምበሮቹ ስምና ሌሎቹም ማስረጃዎች ይገኛሉ። ቀደም ብለው የነበሩት ሁለት ወምበሮች ቤጋባ እና አደክል ቅማንትኛ ስም ሲኖራቸው ከቅርብ

ጊዜ ወዲህ የነበሩት ግን የአማርኛ ስም ነው የነበራቸው። (ከግል የዘር ሐረግ ቆጠራ እንደምንረዳው ቅማንቶች የአማርኛ ስም መጠ ቀም የጀመሩት ከአራትና ከአምስት ትውልዶቸ በፊት ማለትም ከ1800ዎቹ እስከ 1850 ዓ.ም. እ.ኤ.አ. ባለው ጊዜ ውስጥ ነበር።) ይህም የሚያሳየው ቅማንቶች የአማራን ባህል መቀበል የጀመሩት የአማራን ባህል እንዲቀበሉ ከተሰበኩበት ጊዜ በፊት መሆኑን ነው።



ወምበር ሙሉነህ መርሻ፣ የቅማንት ዋናው የፖለቲካና የሃይማኖት መሪ።

አንድ የጭልጋ ወምበር እ.ኤ.አ. በ1889 ዓ.ም. ተመ ርጠው በምትካቸው ደግሞ ሌላ ተተኪ ወምበር እ.ኤ.አ. 1929 ዓ.ም. እንደተመረጡና እስከ እ.ኤ.አ. 1941 ዓ.ም. ካገለገሉ በኋላ ከዚህ ዓለም በሞት ሲለዩ የአሁኑ ወምበር ሙሉነህ መርሻ ተመርጠዋል:: በዚያን ጊዜ ዕድሜያቸው ብቁ እስኪሆን ድረስ አባታቸው በሞግዚትነት ሥራውን ያከናውኑላቸው ነበር:: በወቅቱ በክርስቲ ያንነት ያልተጠመቁ አምስት መቶ ያህል ተከታዮች ነበሯቸው::

አንድ ወምበር ከተመረጠ በኋላ በሕዝቡ ይመረቃል:: ነባሩ ወምበር በሞት ምክንያት ያልተተኩ ከሆነ ከሕዝቡ ጋር ሆነው አዲሱን ወምበር ይባርካሉ:: ሲመረቅ ለልምላሜ ችግር ፍቱን ነው ተብሎ ስለሚገመትም በእጩው ወምበር ላይ እርጥብ አረንጓዴ ሣርና ቅጠል ይርከፈከፍበታል:: በመቀጠልም ሕዝቡ «መሬት የተባረከች ትሁን፣ ሰላም፣ ፍቅር፣ ሲሳይና ጤና ይስጠን» ይላል:: ቀጥሎ ተመራጩ በወምበሩና በአዛውንቱ ቀሳውስት ትምህርት ይሰጠዋል:: ቦታውን ከመረከቡ በፊት ትምህርቱን በሚገባ ማጠ ናቀቅና ነባሩ ወምበር ከዚህ ዓለም በሞት እስከሚለይ ድረስ መጠ ባበቅ ይኖርበታል:: ኃላፊነቱን የሚረከብበት ወቅት ሲደርስ ወደ አንድ ድግና ሄዶ ነጭ ጥምጣሙ ይባረክለታል:: በማግስቱ ሁለት ዓይነት ሌሎች ሥነሥርዓቶች የሚካሄድበት ቀን ይሆናል:: አንዱ ሥነሥርዓት ወደ ኀነት ሊያስገባ ይችላል ተብሎ የሚገመተው «የቁም ተስካር» ሲሆን ሌላው ደግሞ ወምበሩና ቀሳውስቱ ክህነት ሲቀበሉ የሚደረገው «የካሣ» ሥነሥርዓት ነው:: ከነዚህ ሥነሥርዓቶች በኋላ ወምበሩ በቀሳውስቱና በሕዝቡ ላይ ሥልጣን ይኖረዋል:: ከዚያም የጭልጋ ወምበር ስጦታዎችን በመያዝ ወደ ከርከሩ ወምበር ተጉዞ በክብርዋ ድግና በሚደረግ ሥነሥርዓት ሹመቱ ይመረቅለታል፤ በረከተ ፀጋውንም ይቀበላል:: ከክብረ-በዓሉ በኋላ እስከ ሦስት ቀን የሚደርስ ጉብኝት አድርጎ ለጭልጋው ወምበርና አጃቢዎቹ ሁሉ የምግብና የመጠጥ ድግስ በከርከሩ ወምበር ተደርጉለት የበዓሉ ፍፃሜ ይሆናል:: እዚህ ላይ በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመንና ከዚያም ቀደም ብሎ የጭልጋው ወምበር የበላዩ የሆነውን የከርከርን ወምበር በየዓመቱ ስጦታ ይዞ በመሄድ መጠየቅ ባህላዊ ግዴታው እንደነበር እንረዳለን::

እያንዳንዱ ቤተሰብ የአንድ ሰው ጉልበት በዓመት ሶስት ቀን በአካባቢው ላለው ወምበር መስጠት ነበረበት:: ይኸውም አንድ ቀን ለእርሻ፣ ሁለተኛው ቀን ለአረሞና ቀሪው ሦስተኛው

ቀን ደግሞ ሰብል ለመሰብሰብ የተመደበ ነው። ባለፉት አሰርተ ዓመታት ቅማንቶች ለወምበሩ ይከፍሉት የነበረው ግብር በመቋረጡ ዋናው የገቢ ምንጩ ከሕዝቡ የሚሰጠው የጉልበት አገልግሎት ነው። በተረፈ ወምበሩ ለሚያካሂዳቸው ጥቃቅን ሥነሥርዓቶች አሞሌ ጨው፣ ከፍ ላሉ ሥነሥርዓቶች ደግሞ እህልና ከብት ይሰጠዋል። እንዲሁም ለድግስ ከብት ወይም በግ ሲታረድ አንድ የኋላ እግር ሙሉ ነቀላውን መስጠት ባሕላዊ ግዴታ ነበር።

ከፍተኛና ዝቅተኛ ደረጃ ያላቸው ቀሳውስት። ከወምበሩ ቀጥሎ ሁለት የተለያየ ደረጃ ያላቸው ቀሳውስት አሉ። «ከመዘና» እየተባለ የሚጠራው ከፍተኛ ቄስ ከ«ክብር» ዘር የሚመረጥ ሲሆን «አባጋሪያ» እየተባለ የሚታወቀው ዝቅተኛ ቄስ ደግሞ ከየታንተ ዘር ይመረጣል። እንደወምበሩ ሁሉ ቀሳውስቱ የሚመረጡት ከጥንት ጀምሮ የሃይማኖት መሪዎች ከሚወጡበት የዘር ሐረግ ካላቸው ጉማዎች ነው። አንድ ሰው ለቅስና ብቁ ይሆናል ተብሎ ከተመረጠ በኋላ ሕዝቡ ወደ ወምበሩ በማቅረብ እንዲባረክና ሹመቱ እንዲፀድቅለት ይደረጋል። ለዚሁ አገለግሎት ወምበሩ ሁለት አሞሌ ጨው ወይም ሁለት ማሪያ ቴሬዛ ብር ይሰጠዋል። ከዚያም ቀጥሎ ቄሱ ሥራውን መለማመድ ይጀምራል። መሠረታዊ የሆነውን ሥልጣን የሚያገኘው በሃይማኖታዊ ሥነሥርዓቶች ላይ አዘወትሮ ተገኝቶ በመለማመድ ነው። ከጥቂት ዓመታት በኋላ ቄሱ ወደ ወምበሩ ይሄድና የተባረከውን ነጭ ጥምጣም ያገኛል። በመጨረሻም እንደወምበሩ የ«ካሣ» እና የቁም ተዝካር ሥርዓተ-ቅዳሴ ተደርጉለት የካህንነት ደረጃ የመስጠቱ ሥነሥርዓት ይፈጸማል። ወምበሩ ከአንድ አሞሌ ጨው እስከ አንድ ላም ወይም በሬ የሚደርስ መቀጫ በመጣል የቀሳውስቱን ሥነምግባርና ሥራቸውን በአጠቃላይ ይቆጣጠራል።

ማንኛውም ኅብረተሰብ የዕለት ተዕለት ሃይማኖታዊ ተግባሮችን የሚከታተልለትና የሚያስፈጽምለት ቢያንስ አንድ ከፍተኛና አንድ ዝቅተኛ ቄስ ይኖሩታል። አንድ መስዋዕት በሚባረክበት ጊዜ ከፍተኛው ቄስ በሬ ወይም በግ ወይም ዶሮ ሲያርድ ፣ ዝቅተኛ ቄሶች የእንስሳውን እግር መያዝ



ከመዝሙሩ ወይም ከፍተኛው የቁልጋ ቄስ ጋቢ ደርበውና ጥምጥማቸውን አድርገው በእጃቸው ነጭ የፈረስ ጭራ እንደያዙ።

ይኖርባቸዋል። እያንዳንዱ ቄስ በጋራም ሆነ በተናጠል በቅዳሴ የመሳተፍ ድርሻ አለው። በተጨማሪም ዝቅተኛው ቄስ

በሥነሥርዓቱ ላይ በገና ያሰማል። ሁለቱ ቄሶች በአንድ ላይ ሆነው የአየሩን ጠባይ ለመቆጣጠርና እንስሳትም ከበሽታቸው እንዲፈወሱ ጸሎት ያደርሳሉ። እንስሳት ሲታመሙ ከብቶችን በአንድ ላይ ሰብስበው ይጸልያሉ። ይህ ጸሎት በሚደረግበት ወቅት አንደኛው ቄስ አንድ በግ በእቅፉ ይዞ በከብቶች ዙሪያ ካዞረው በኋላ በጉ ይታረድና ደሙ በከብቶች ላይ ይረጫል።

ቀሳውስቱ በኑዛዜ ሥነሥርዓት፣ ዝናብ እንዲስተካከልና ስለከብቶች ጤንነት ይጸልያሉ። ለሚያደርጉት የጸሎት ሥነሥርዓቶች ክፍያው በአሞሌ ጨው ነው። ዋናው የገቢ ምንጫቸው ግን ከእያንዳንዱ ቤተሰብ አንድ ጉልማሳ ለቀሳውስቱ ከሚሰጠው የጉልበት አገልግሎት ነው። እንደወምበሩ እያንዳንዱ ቄስ በዓመት ከአንዱ ቤተሰብ የሦስት ቀን ጉልበት ሥራ ማለትም አንድ ቀን ለእርሻ፣ አንድ ቀን ለአረሞ ሌላው አንድ ቀን ደግሞ ለሰብል ስብሰባ የሚውል አገልግሎት (ኩዳድ) ያገኛል። ከዚህም በስተቀር ምንግዜም ቢሆን የኅብረተሰቡ አባል ድግስ በሚደግስበት ጊዜ ቀሳውስቱ በግብዣው ላይ በመገኘት እንደፈለጉ መመገቢ ይችላሉ።

<u>አነስተኛ የፖለቲካና የሃይማኖት ነክ ሹመት</u>። ከሃይማኖትና ፖለቲካው ጋር ግንኙነት ያላቸው፣ ነገር ግን ከቅስናው ዓለም ጋር ግንኙነት የሌላቸው ሦስት የሥራ መደቦች አሉ። ከእነዚህም በጣም ከፍተኛ ግምት የሚሰጠው ከክብር የዘር ሐረግ በወምበሩ ተመርጦ የሚሾመው አፈሊቅ (ቃል አቀባይ) እየተባለ የሚጠራው ነው። ዋና ተግባሩ ወምበሩ በሚሰጠው መመሪያ መሠረት አንዳንድ ምርመራዎችን በማጣራት ለጭቅጭቆች መፍትሄ መፈለግ ነው። ማጣራት የሚደረግባቸው ጉዳዮች ብዙ ጊዜ በገበሬዎች መካከል የእርስ በእርስ ግጭቶችና የአረማዊው-አሪታዊው ሕግ መጣስ ሲያጋጥሙ ነው። ሌላው የሥራ መደብ ደግሞ በክብረ-በዓል ቀን የዋናው አስተናጋጅነት (ጋላሲሞ) ሥራ ነው። ይህም ከክብር የዘር ሐረግ ካለው የሚመረጥ ሆኖ ዋና ተግባሩ ለክብረ-በዓል የተዘጋጀውን ጠላና የሽምብራ ቂጣ (ሻምኩራ) በሚገባ ለሕዝቡ በትክክል እንዲዳረስ ማድረግ ነው። ምግቡ በቂ ካልሆነ በተጨማሪ ሕዝቡ ምግብ እንዲያቀርብ ማዘዝ ሥልጣን አለው። ሦስተኛው የሥራ መደብ ደግሞ «ማሻና» ይባላል። ኃላፊነቱ «መስኪ» የተባለውን የተባረከ

ጠላ ወደ ሥነሥርዓቱ ቦታ አምጥቶ መቅዳትና ማከፋፈል ሲሆን ከየታንቲ የዘር ሀረግ የሚመረጥ ነው።

# ምዕራፍ አምስት

## ከቅማንት እግልዕክትና ከቅስናው ዓለም ውጭ ያሉ መናፍስትና ባለሚሉቻቸው

የግል መናፍስት፣ ቆሊዎች፣ ጂኒ እና ሌሎች ከዚህ በታች የምናያቸው ልዩ ልዩ የበሽታ መናፍስት በቅማንት፣ በሌሎች አገሮች፣ በክርስቲያንና በእስላም አማራዎች ዘንድ የታወቁ ናቸው:: ስለመናፍስት አመጣጥ በቅማንቶችና በሌሎች ጉረቤት በሆኑ ሕብረተሰቦች የሚነገር ተረት አለ:: ይኸውም:- አዳምና ሔዋን ብዙ ልጆች እንደነበሯቸውና ከእለታት አንድ ቀን እግዚአብሔር ሄዋንን ልጆቿን በሙሉ እንዲያሳያት ሲጠይቃት ሌሎቹን ደብቃ ሠላሣዎቹን ብቻ ታሳየዋለች:: እግዚአብሔርም በዚህ ተቆጥቶ «የደበቅሻቸው ልጆችሽ ለዘለዓለም ተደብቀው ይኑሩ፣ ያሳየሽኝ ልጆችሽ ደግሞ ሁልጊዜ የሚታዩ ይሁኑ» አላት ይባላል:: ሌላው ዓይነት ትረካ ደግሞ አዳምና ሔዋን አስራ አምስት ቆንጆ ልጆችና አስራ አምስት አስቀያሚ ልጆች እንደነበሯቸውና አንድ ቀን እግዚአብሔር ሔዋንን ልጆቿን እንድታሳየው ሲጠይቃት ቆንጆዎቹን ልጆች ደብቃ አስቀያሚዎቹን ስላሳየችው እግዚአብሔር ተቆጥቶ የደበቀቻቸውን ልጆች፣ በጨለማና በጥላ ውስጥ እንዲኖሩ ረገማቸው ይባላል:: እንደትረካው የሚታዩት ልጆች የአሁኑ የሰው ልጆች ጥንታዊ ትውልድ ሲሆኑ የተደበቁት ግን በጨለማ፣ በውሃ ውስጥ፣ በሰዎች ላይ ተሣፍረው የግል ቆሊና መናፍስት ሆነው እንዲኖሩ ተደረገ ነው የሚባለው:: አንዳንዶቹ መናፍስት ሰዎችን የሚጠብቁና ስለደጎንነታቸውም ለእግዚአብሔር የሚጸልዩ ናቸው ይባላል::

## ዛር፣ የግለሰብ ውቃቢ

ቃልቻነት:: ሃምሣ አራት ዓመት ዕድሜ ያለው የአቶ ረዳ ወንድም፣ እዮ እንደሌላው ቅማንት ሁሉ ዋና ሥራው ግብርና ቢሆንም በትርፍ ጊዜው የቃልቻነት ሥራ ይሠራል:: እዮ፣ ዛርና የግል ውቃቢ ላላቸው ሰዎች የዛር አለቃ በመሆን ከአቶ ረዳ ቤት አንድ ሺ ሜትር ርቆ ከሚገኘው ቤቱ አጠገብ አንድ ልዩ ቤት ውስጥ የቃልቻ ሥራውን ያከናውናል:: ባለዛሮች ከሌሎች የአገው ዘር፣ ከክርስቲያን ወይም ከእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች ሊሆን ቢችልም የማንኛውም ሃይማኖት ቁስ ግን አይሆንም:: በሕዝቦች

ዘር አጥኚዎች (አንትሮፖሎጂስት) አመዳደብ ባለዛር ከልዩ ልዩ መናፍስት ጋር በመገናኘት ልዕለ-ፍጡራዊ ተግባሮችን ለማከናወን የሚሞክር በቃልቻነት የሚመደብ ሰው ነው:: እነዚህ እነስተኛ ውቃቢዎች (መናፍስት) ሲሆኑ በባለዛሩ ላይ ሲሠፍሩ ሰውዬውን የእነሱ ቃል አተባይ ያደርጉታል:: የቅማንትና የሌሎች ጉረቤቶቻቸው ቃልቻዎች ብዙ ጊዜ የባለውቃቢዎች መሪ ናቸው::

ቃልቻነት በቴክኖሎጂ ኋላቀር በሆኑ አዳኞችና ፍራፍሬ ለቃሚ በሆኑና በዝቅተኛ እርሻ ላይ በተሰማሩ ዝቅተኛ ኅብረተሰቦች የተለመደ ነው:: ቅስና ግን በቴክኖሎጂ በገፋና ይበልጥ ውስብስብ በሆነ ማኅበራዊና በእርሻ ኤኮኖሚ በተደራጁ ኅብረተሰቦች ውስጥ የሚከሰት ሥርዓት ነው:: በቅማንት አገር እንደ አዮ ያሉት ባለዛርና ዛር መሰል የግል ውቃቢ የአገው ሕዝብ የቅስና እና የአማልእክት ሥርዓት ከመመሥረቱ በፊት የነበሩ የጥንታዊው የአገው ትውፊቶች ናቸው:: በዚያ ጥንታዊ ዘመን «የሰማዩ እግዚአብሔር» በጣም ስለሚርቅባቸው ትኩረት የሚሰጠ ው በቅርብ ለሚገኙት ቃልቻዎችና ዝቅተኛ ውቃቢዎች ነበር:: ይህ ዓይነቱ የቃልቻ እምነት አደረጃጀት ሥርዓት እስከ ቅርብ ጊዜ ድረስ በኩምፌል አገሮች ተግባራዊ ሲሆን የቆየ ነው:: በአንዳንድ ምሑራን አስተያየት ይህ «የሰማዩ እግዚአብሔር» ዛር እንደነበርና ቆይቶም ደረጃው ወደ ቆሌ ወይም ውቃቤ (መንፈስ) ዝቅ ብሎ እንደወረደ የሚነገረው በተጨባጭ ማስረጃ ባለመደገፉ ተቀባይነት የለውም::

በቅማንትና በጉረቤቶቻቸው ዛር ከሁሉም መናፍስት በጣም የታወቀ የግል ውቃቤ ነው:: አንድ ግለሰብ አንድ ዛር ወይም ከዚያ በላይ ሌሎች የግል ውቃቤዎች ሊኖረው የሚችል ቢሆንም አብዛኛው ሰው ግን ምንም የለውም፡ ያላቸውም ቢሆኑ ዛሩ ለወራት፣ ለዓመታት ላይሾም ይችላል:: ዛር ወንድ ወይም ሴት ሊሆን ይችላል:: አብዛኛውን ጊዜ ግን ዛሩ የሚይዘው እንደያታው ነው:: እንደየሁኔታው ዛር ደግ ወይም ገለልተኛ (አድፋጭ)፣ ነገር ግን ሳይንከባከቡት ከተውት ተንኮለኛ በመሆን በሽታና ሌሎች መጥፎ ዕድሎችን ሊያስከትል ይችላል:: ዛር ግለሰቡን በቀጥጥሩ ሥር በማድረግ ያስጉራዋል፡ ያስለፈልፈዋል:: ምንም እንኳን ሁሉም ቅማንት ዛር መኖሩን ቢያምኑም ወምበሩና ቀሳውስቱ ከውቃቤ ጋር የተያያዘ የቅዳሴ ሥነሥርዓት እንዲካሄድ አይደግፉም፡ አይፈቅዱም:: እንደሌሎች የዛር አለቆች ሁሉ የአዮ

ዛር ከግለሰቦች ዛር የበለጠ ኃይለኛና አዋቂ ነው። በመሆኑም በሰዎች ላይ ተፅዕኖ ማድረግ የሚያስችለውን እውቀትና ማስረጃ ከሌሎች ውቃቢዎች ማግኘት ያስችለዋል። ይህን ችሎታ ሊያገኝ የቻለው ከአንድ ዘመዱ የነበረውን ውቃቢ በመውረሱ ነው። ሌሎችም ባለውቃቢዎች ለዘመናት ኃይለኛ የሆነ ውቃቢ ይዘው ከቆዩ ወደ ቃልቻንት ደረጃ ይሸጋገራሉ።

ረጅምና ቀጥ ያለ ቁመና ያለው አዮ ሸበቶና ራሰ-በራ ነው። ይህን የቃልቻ ሥነሥርዓት በሚያካሂድበት ጊዜ ልዩ የሆነ ነጭ ልብስ ይጐናፀፋል። አንዳንድ ቃልቻዎች ደግሞ ደማቅ ቀይና ቢጫ የሆነ ግምጃ ይለብሳሉ። ረዥም የሆነ ጨሌ በአንገታቸው ያጠልቃሉ፤ በአብዛኛው ጣቶቻቸው ቀለበቶች አሏቸው፤ ፀጉራቸውን ያጐፍራሉ፤ እንዲሁም በሰውነታቸው ላይ አንድ ወይም ሁለት ደውሎች ያንጠለጥላሉ። ብዙ ጊዜ አነስተኛ የብረት ዘንግ ወይም የእንጨት እጀታ ያለው ጭራ ከእጃቸው አይለይም። በአጠቃላይ ሲመለከቷቸው ቃልቻዎች በአሜሪካ ዩኒቨርስቲዎች ከቅርብ ጊዜ ወዲህ የሚታዩትን «ሂፒዎችን» ይመስላሉ።

አንዳንድ ከውቃቢያቸው ጋር የተጣሉ ሰዎች ወይም ከራሳቸው ጋር ያልተለማመደና ያልተግባባ አዲስ ውቃቤ የተሳፈረባቸው እንደሆነ ወይም ከዛር ጋር የተዛመደ ወይም ያልተዛመደ አንዳንድ መረጃዎችን ለማግኘት የሚሹ ሰዎች ወደ አዮ ቤት ይመጣሉ። እንደ አዮ ያለ የታወቀ ቃልቻ ቡና የሚያፈላ፣ እሳት የሚቆጣጠርና ሥነሥርዓት የሚካሄድበትን የቃልቻ ቤት አስተካክሎ የሚይዝ «ከዳሚ» የተባለ አገልጋይ ይኖረዋል። እንደሌሎቹ ቃልቻዎች ዛር የያዛቸው ሰዎች ዛሩ የሚሾምበትን (የሚወርድበትን) ምሽት ቀጠሮ ይይዛል፤ ነገር ግን የዛር ሥነሥርዓት ሊካሄድ የሚችለው ወደ ምሽቱ ቢሆንም በእርግጥ ዛር የተሣፈረበት መሆኑና ሊወርድም ዝግጁ መሆኑ ሲረጋገጥ ነው። ስለዚህ አዩ አስቀድሞ በቀን ይህን ግለሰብ ማየት አለበት። በቀን ቀጠሮው የአዮ ዛር ይወርድና ከግለሰቡ ዛር ጋር በአፈ-ቀላጤ ነት ይነጋገራል። አንዳንድ ጊዜም የሰውየው ዛር እንዲወርድ ያግባባና ዛር ለዛር ይነጋገራሉ፤ ወይም በሽተኛው ደካማ ከሆነ አዮ ወደ ደምበኛው ቤት በመሄድ አገልግሎት ይሰጣል።

ቃልቻው ለሚሰጠው አገልግሎት ቡና፣ ምግብ፣ አረቄና ገንዘብ በስጦታ መልክ ያበረክቱለታል። አንድ ግለሰብ ከአንዱ

ቃልቻ ተገቢውን ፈውስ ካላገኘ ወደ ሌላው ቃልቻ ይሄዳል። ከአንዱ ቃልቻ ወደሌላው ለብዙ ጊዜ ሲሄዱ ቆይተው ከበሽታው ሳይፈወሱ የሚሞቱም አሉ። ጥቂት ደንበኞች ከአዮ ጋር ለብዙ ዓመታት ቆይተው ሌላ ደንበኛ የተከኑም አይጠፉም። በቅርቡ አንዲት የሴት ቃልቻ ከጉረቤት ካለ ኀብረተሰብ ብቅ በማለቷ አዮን እየተው ወደ እርሷ እየጐረፉ ናቸው።

የቃልቻው ሥራ በምሽት ተጀምሮ እስከ እኩለ ሌሊት ይዘልቃል። አስቀድሞ በተሰጠ ማሳሰቢያ መሠረት ደንበኞች እንደተሰበሰቡ አዮ በመጋረጃ ተከልሎ በወንበር ወይም በአርጩሜ ላይ ይቀመጣል። ዛር የተሾመባቸውንና ያልተሾመባቸውን አዲስ ጀማሪዎችን ለመለየት በአለንጋ ይገርፋቸዋል፤ ወይም በሹል ነገር ይወጋቸዋል፣ ወይም ደግሞ በእሳት ምድጃ ላይ እንዲንከባለሉ በማድረግ ቃጠሎው ወይም ሕመሙ ያልተሰማቸው ከሆነ በትክክል ዛር የተሳፈረባቸው መሆኑን ይለያል። ከዚህ ሥነሥርዓት በኋላ ዛር ተሳፍሮባቸዋል ተብለው የተለዩት የተሰብሳቢዎቹ አባል ይሆናሉ። ያልፀዱ ማለትም ባለፈው ሌሊት ግብረ-ሥጋ የፈፀሙ ወይም ከወር አበባቸው ያልፀዱ ሴቶች ወደ ቃልቻው ቤት መግባት አይፈቀድላቸውም።

<u>በዛር አለቃው ቤት</u>፡፡ የምሽቱ ሥነሥርዓት በሚካሄድበት ጊዜ የመጋረጃው ግርዶሽና አደናጋሪ የሆነው «የዛር ቋንቋ» ግርግር ሁሉ ተሰብሳቢዎች በፍርሃት ተውጠውና ተወናብደው ስለቃልቻው ሚስጢራዊ ሥራው ምንም ዓይነት ጥያቄ እንዳያነሱ የተደረገ ሽፋን ነው። የአዮ ደንበኞች ከምድጃው በሚነደው እሳት ጭላንጭል እየተያዩ በጭቃና በጨፈቃ በተሠራው ቤት ውስጥ እርጥብ ሣር በተጉዘጐዘ ወለል ላይ ተኮልኩለዋል። አዮ በመጋረጃ ተሸፍኖ በታዳሚዎች በሚደረገው ጭብጨባና የራሱን የዛር ዘፈን አጅቦ በሚደለቀው ድቢ (ከበሮ) ግድግዳዎች እየተንቀጠቀጡ ነው። የድቢውን ምት ተከትለው ሰዎቹ ሁሉ ያጨበጭባሉ፣ ከእርሱ ጋርም አብረው ያዜማሉ።

በዚያች በሰዎች በተጣበበች ቤት ከባድ የሆነው የቡናና የዕጣን ጭስ ሽታ እራስ የሚያዞር ነው። ከዚህም በስተቀር የሚያጉረመርመው የሰው ድምፅ ከሚጠጣው አረቄና ከሚታኘከው ጫት ጋር ተደበላልቆ ሁኔታውን ልዩ ያደርገዋል። ዛር ያላቸው ሰዎች ዛሩ ወርዶ ማጉራት ይጀምራሉ። አንድ ሰው በአንድ ዛር

ወይም በተከታታይ በሚሸሙ ዛሮች ሊያዝ የሚችል ቢሆንም በአንድ ጊዜ ከአንድ በበለጠ ዛር አይያዝም።

አዮ ከእያንዳንዱ ግለሰብ ዛር ጋር በዛር ቋንቋ እየተነጋገረ እንደገና በመተርጐም ግለሰቡ ዛሩን ለማስደሰት ምን መፈጸም እንዳለበት ያስረዳል። ዛር የተሾመበት ሰው በራሱ ቋንቋና እንዲሁም ልዩ በሆነ ድምፅ በዛር ቋንቋ ይናገራል።

የዛር ቋንቋ ይለያያል። የእስልምና ሃይማኖት ተከታይ የሆነ ቃልቻ ከቁርዓን አንዳንድ ብዙ ሊገቡ የማይችሉ ሐረጉችን በመጠቃቀስ ለመናገር ይሞክራል፣ የአንዳንድ ሰዎች ዛር ደግሞ ብዙ ለመረዳት በማይቻል ሁኔታ በመንተባተብ አሮምኛ በመሰለ ቋንቋ በመዘበራረቅ ለመናገር ይሞክራል። የሌሎችን ስንመለከት ከሁሉም ቋንቋ የተለያዩ ቃላትን በመውሰድ የራሳቸውንም አክለውበት ይንተባተባሉ። አዮ ከንፈሩን ሳያንቃንቅ ከተለያዩ ጓዳዎች ሆኖ የዛሩን ድምጽ ያሰማል። ዛሩ የተሰበሰበው ሕዝብ እንዲዘፍንለት፣ መጠጥ እንዲያመጡለትና ሌሎችም ነገሮች እንዲያደርጉለት ይጠይቃል። በሁሉም ነገር ከተደሰተ ዛሩ የተሰበሰበውን ሕዝብ መርቆ «ፈረሱን» ትቶት ይሄዳል።

አንድ ቀን ምሽት ላይ በዛር አለቃው ቤት ሰዎች እንደተሰበሰቡ አንዲት የተንቀገፐቀገፐች መካከለኛ ዕድሜ ያላት ቆንጆ ሴት የእንብርክክ እየሄደች ያገኘችውን ሁሉ በጥርስ መንከስና ማኘክ ጀመረች። የሁሉንም ጨርቅና ካገኘችም እጅና እግር አይተርፋትም ነበር። በኋላም መሬት ላይ ተንሠራፍታ ተቀምጣ «አረቄ አምጡ!»ብላ ጮኸች። ለዛሯ የተቀዳውን አረቄ ከተጐነጨች በኋላ ዛሯ በከፍተኛ ድምፅ ለተሰበሰበው ሕዝብ «ጠላቶቻችሁ ዐመድ ይሁን፣ ቆሌው ሀብቱን ይስጣችሁ፣ የበላይ አለቆቻችሁን ያራራላችሁ፣ ኃይሉን ይስጣችሁ፣ ምቀኞቻችሁ ይጥፉ» በማለት አመሰገነ። በኋላም የሴትየዋ ዛር ውሃ ጠየቀ። አዮም ሣር የተርከፈከፈበት ውሃ በሳህን ተሞልቶ ከቤቱ በር እጠገብ ካለው ወለል እንዲቀመጥ እንዳደረገ ሴትዬዋ በእንብርክክ ወደ ውሃው ሄዳ በጥርሷ ውሃ ያለበትን እቃ አነሣችና ግጥም አድርጋ ጠጣችው። ከዚያም ተነስታ ከፍተኛ የሙጓጐር ድምጽ በማሰማት እያጓራች ለአምስት ደቂቃ ስትሽከረከር ቆይታ በእጅዋ የሚነደውን እሳት እንደነካች መሬት ተዘርራ በተረጋጋ መልክ አርፋ ተቀመጠች። ከዚያ በኋላ የአዮ ድቢ ሥራውን

ቀጥሎ ካዳሚውም እሳቱን ስለቆሰቆሰው ተያይዞ መን ጣጣት ጀመረ::

ሌላዋ ዛር የተሳፈረባቸው ሁለተኛዋ ሴት ደግሞ ባላቸውን የፈቱ ጠና ያሉ ሴት ነበሩ:: ወለሉ ላይ ደህና ተቀምጠው ሳለ ድንገት ሰውነታቸው ተኮማተረና ከመጣጣ ፊታቸው ያሉት ሁለት ዓይኖቻቸው ፈጥጠው ቀሩ:: ወንድ ዛር ነበርና የያዛቸው እንዲህ አለ፣ «አሁን ሌሊት ሆኗልና ሕዝቡ በጭብጨባና በድቤ ያስደስትኛል::» ቀጥሎም ከድቤው አነስተኛ ድምፃና ከእሳቱ መንጣጣት በስተቀር ፀጥታ ሠፈነ:: አዮ የዛር ተከታዮቹን እንዲያጨበጭቡና የሴትየዋን ዛር እያሞገሱ እንዲዘፍኑ አዘዘ:: ዛሩ አረቄ እንዲሰጠው ጠየቀና እሩብ ጠርሙስ የሚሆነውን ሴትዮዋ ከጨለጠች በኋላ ወፍራም ቡና አከላበት ዛሩ ምንም ቃል ሳይናገር ለቋት ሄደ::

አሮጊቷ እራሳቸውን አውቀው ከሁለት ደቂቃ ቆይታ በኋላ ደግሞ ሌላ ሴት ዛር ተሣፈረችባቸው:: ለረዥም ጊዜ አዮ በዛር ቋንቋ ውይይት ካደረገ በኋላ ለዛሯ ተብሎ የተፈላው ቡና ተጠ ጥቶ እንዳበቃ ኃይለኛ ጩኸት በማሰማት ለቀቃቸው::

ከትንሽ ደቂቃ በኋላ ሴትየዋ ፀጥ ብለው እንደተቀመጡ ሌላ ወንድ ዛር ስለተሳፈረባቸው ሰውነታቸው መንቀጥቀጥ ጀመረ:: ግልጽ በሆነ አነጋገር፣ «ይህች ሴት ጌጣጌጤንና ልብሴን እንድታመጣ ባለፈው ጊዜ መጥቼ ሳለ የሰጠሁትን ትእዛዝ ስላልፈፀመች አሁን እንድትገዛልኝ» አለ:: አዮም ይህንኑ ትእዛዝ እንድትፈጽም የሚያደረግ መሆኑንና ወንድሞቿም የተባለውን ጌጣጌጥ በመግዛቱ ረገድ እንዲረዷት አሳስቦ ከዚያም የአንድ ጠር ሙስ አረቄ ስጦታ ከተሟላለት በኋላ ዛሩ ለቋቸው ሄደ:: የአንዳንድ ሰዎችን ዛር ኃይለኛ የሆነው የአዮ ዛር ከአስተናገደ በኋላ ስብሰባው ተበትኖ ሌሊት በጠፍ ጨረቃ ሁሉም ወደ እየቤቱ አመራ::

<u>ዛርና ግለሰቡ</u>:: የግል ዛር ተቆጥቶ በጤንነትና በሀብት ላይ ችግር እንዳያስከትል በተቻለ መጠን ለማስደሰት እንክብካቤ ማድረግ ያስፈልጋል:: አንዳንድ ጊዜ አንድ ግለሰብ ብቻ ሳይሆን ዛሩን ለማስደሰት የመላ ቤተሰቡ ኃላፊነት የሚሆንበት ጊዜ አለ:: በጋራ የሚደረግ ስጦታ በተመሳሳይ ሁኔታ ከዚህ በታች

እንደተገለፀው ለሌሎች መናፍስትም ይሰጣል። ለመድኃኒት የሚሆኑ የተለያዩ ቀለማትና መልክ ያላቸው እንስሳት ለምሳሌ እንደበግና ዶሮ የመሳሰሉት መስዋዕት ተደርጉ ሥጋቸው በአትራቢያው ባሉ ሰዎች፣ በቤተሰቡና በጓደኞቹ ይበላል። ለመድኃኒት ተብሎ በተለይ የሚረቡ የተለያዩ እንስሳት ግልገሎቻቸው፣ ዶሮም ከሆነች እንቁላሏ ተሸጦ ለዛሩ ስጦታ ይሆናል። ደማቅ ቀለም ያለው ልብስ መልበስና አረቂ መጠጣትም ለዛሩ እንደስጦታ ይቆጠራል።

በመንፈስ መያዝ በተለይም ከዚህ ዝቅ ብሎ በተገለፀው ዓይነት በጥንቆላና በአስማት መካፈል አንዳንድ ጊዜ ተስፋ ከመቁረጥና አለመግባባት እንዳይፈጠር ይረዳል። ግለሰቦች ከጐረቤትና ከቤተሰብ ጋር የነበራቸው የጥላቻ መንፈስ እንዲለወጥ በማድረግ ሊደርስ ይችል የነበረውን ግጭት ወይም ደም መቃባት ያስቀራል። ይህ ሁኔታ ቢፈጠር ምን ዓይነት ማኅበራዊ ቀውስ ሊያስከትል እንደሚችል መገመት አያዳግትም። ይህም በመሆኑ በቃልቻ መጠቀም የቅማንት ኅብረተሰብ የማኅበራዊና ሥነ ልቦናዊ ችግሮች መፍቻ አንዱ ሆኖ በመቆየቱ የኅብረተሰቡ አንድነትና ሕልውና ተጠብቆ እንዲቆይ ረድቷል ለማለት ያስደፍራል።

አንድ ዛር በፈረሱ (ዛሩ በተሳፈረበት ሰው) ላይ የደረሰውን በደል፣ ስድብ ወይም ስለንብረት ክርክር ሊሆን ይችላል፣ ወይም ግለሰቡ ሳይረካ የቀረበትን ፍላጐት በቃላት ይገልጻል። ለምሳሌ የቢተው ዛር የድሮ ተቃራኒውን ቢያዋርድ ወይም ስለአንዲት የደረሰች ቆንጆ ልጃገረድ ፍቅሩን ቢገልጽ ቢተው ለጥፋቱ ተጠያቂ አይሆንም። ቢሆንም የቢተው ጠላት ስለተሰጠው አስተያየት ግንዛቤ በማግኘት ጥንቃቄ ያደርጋል፤ የጐረቤቷ ልጃገረድም ቢተውን በመንገድ ላይ በምታገኝበት ጊዜ መሽኰርመሟ አይቀሬ ይሆናል።

አልፎ አልፎ በኅብረተሰቡ የሚወራውና ያለውን ስሜት በማሰባሰብ ቃልቻው ስለደምበኛው በሕዝብ ፊት በግልጽ ይናገራል። ለምሳሌ «የአዮ ዛር ስለሚግባባኝና ፍላጐቴን ስለሚያሟላልኝ ዘውትር ወደእርሱ እሄዳለሁ» ይላል።

ቃልቻነት ለአንዳንድ ዋልጊና ሥራ-ፊቶች፣ በሥራ ዓለምም ተስማርተው ኑሮው አልሳካላቸውም ላለና በኅብረተሰቡ ዘንድ ተቀባይነት አጥተው ተንገዋለው ለቀሩ የኑሮ ማስተካከያና በማኅበረሰቡም ዘንድ ታዋቂነትን ሊያተርፍላቸው ይችላል:: ቃልቻ የሆነ ግለሰብ ከኅብረተሰቡ እንክብካቤ፣ ቁሳቁስና ገንዘብ ማግኘትንም ሊያስከ ትለለት ይችላል:: በዛሩ ምክንያት የሚገኙ ስጦታዎችና ሌሎችም ጥቅማ ጥቅሞች ዞሮ ዞሮ የሚጠቀሙት ግለሰቡን በመሆኑ ሕሊናው አውቀም አላውቀ የግለሰቡ ፍላጐት ማሟያ መግለጫ ይሆናል::

የወንድ የበላይነት በሠፈነበት በቅማንት ኅብረተሰብ አንዲት ሴት የተወሰነ ዋስትና ለማግኘት ለዛር ተንበርክካ ዛር ተሸካሚ (ፈረስ) በመሆኗ እድሜ ልኳን አብሮ የሚኖሩትን የባሏንና የቤተሰቡን ፍቅር መማረትና ሊላም ነገ የማግኘት እድል ይኖራታል:: ከዚህም በላይ ባሏን የፈታች ሴት፣ ወይም ከባሏ የተሟላ ፍቅር የማታገኝ፣ ወይም ደግሞ ከሌሎች ሰዎች ጋር ግብረሥጋ ለመፈፀም ያልቻለች፣ ወይም ለመፈጸም የተከለከለች ሴት በሚገባ ይንከባከበኛል በምትለው ዛር ትያዛለች:: በዚህ ዓይነት በፈቃደ-ሥጋ የተበደሉ ሴቶች ዛራቸው ሲወርድ አካላዊም ሆነ አዕምሮአዊ የሩካቤ-ሥጋ ያደረጉ የሚመስላቸው ሁኔታ አለ:: በአብዛኛው ጊዜ ከዛር ጋር የሚደረጉ ሥነሥርዓቶች የፈዋሽነት ጠባይ ያለው፣ ጭንቀትን አስወጋጅ፣ ፍላጎትን የሚያረኩና ጥሩ ስሜትን የሚያስገኙ ናቸው ተብሎ ይታሰባል:: ጥሩ ልብስ መልበስ፣ በምግብና በመጠጥ በኩል ሙሉ በሙሉ እርካታን ማግኘት የመሳሰሉት በዛሩ ሰበብ ሊገኙ ከሚችሉት ጥቅሞች አንዳንዶቹ ናቸው::

ባለዛር ትኩረት የሚሰጠውና የሚፈራ ሰው ነው:: ይህን ክስተት በተመለከተ ሲሞን ሜሲንግ ሲገልፀው፣ «ዛር ተስፋ መቁረጥን ጨምሮ እስከ ደንበኛው የአእምሮ በሽተኛነት የሚያደርስ ሁሉ-አቀፍ የሆነ የአእምሮ መረበሽን የሚያስከትል በሽታ ነው፣» ይለዋል:: (1858:1125) :: ከዛር ጋር በፍላጎት መቆራኘትን በተመለከተ ሰዎች በዛር የሚያዙት የቃልቻ ሥነሥርዓት በሚካሄድበት ወቅት ብቻ ሳይሆን በማንኛውም ጊዜ ሊሆን ቢችልም፣ በተለይ ግን ዛር ይሾማል ተብሎ በታመኑበት ቀናት ይሆናል:: በእነዚህ ቀናት በዛር መያዝ ማለት የሚያረካ እንክብካቤን ያስከትላል ተብሎ ይታመናል::

የግል ቆሌ (ውቃቤ)፡፡ ሁሉም ሰው ዛር ባይኖረውም የግሉ የሆነ ውቃቤ ግን አለው፡፡ በምዕራፍ አራት የአካባቢ ቆሌ ብለን ከገለፅነው በኃላፊነታቸው ያነሱ ሲሆን ሁለቱም በዓይን የማይታዩ ረቂቅ መናፍስት ከመሆናቸው በስተቀር ሌላ የሚያመሳስላቸው ጉዳይ የለም፡፡ የግል ቆሌዎች ሰውን አይጠናወቱም፡ ሆኖም፡ ሆነው ከተገኙ የቃልቻን ምክር በመጠየቅ ችግሩ እንዲፈታ ይደረጋል፡፡ የግል ውቃቤ የራስ ደህንነት ጥበቃ ዋስትና ናቸው ተብሎ ስለሚታመን ውቃቤ አለኝ ብሎ ማመን ከማንኛውም ዓይነት ጭንቀት ሁሉ ይጠብቃል፡፡ አቶ ረዳ እንደሚሉት «ከነዚህ አንዱ ዓይነት ውቃቤ የሌለው ሰው ጠባቂ እንደሌለው ሰው ይቆጠራል፡፡» ውቃቤ ወደፊት የሚሆነውን የመተንበይ ችሎታም አለው፡፡ ለምሳሌ አንድ ቀን ወይዘሮ አዳነች የእነሱን ቤተሰብ ለመጎብኘት የእኔንና የረዳቴን መምጣት አሳቱ በተለየ መልክ በመንደድ ውቃቤያቸው አስቀድሞ እንደነገራቸው የገለፁልኝን አስታውሳለሁ፡፡

ብዙ ጊዜ የግል ቆሌ ደግ ወይም ገለልተኛ ነው ቢባልም አልፎ አልፎ በመስዋዕት ካላቆላመጡት ክፉ ጠባይ ሊያሳይ ይችላል፡፡ ጥቂት ቆሌዎች ምንም መታሰቢያ ባይደረግላቸውም ሰላማዊ ሆነው ይኖራሉ፡፡ ግለሰቡ ወይም ቤተሰቡ በሙሉ እነዚህን መናፍስት ለማባበል መስዋዕት ሊያደርጉ ይችላሉ፡፡ ነገር ግን አንዳንድ የውስጥ አዋቂዎች ይህን ማድረግ ከተጀመረ በየጊዜው «አምጡ አምጡ» ማለትን ሊያስከትል ስለሚችል ችግር ካልፈጠረ በስተቀር መስዋዕት ማድረጉን አለማስለመድ የተሻለ መሆኑን ይገልፃሉ፡፡

አቶ ረዳና ቤተሰባቸው ለአንድ ቆሌ መስዋዕት ካቀረቡ ለሦስት ቀን ያህል ከቤታቸው አይወጡም፡፡ ከሌሎች ሰዎች ጋር አይገናኙም፡ እንዲሁም ከሰው ጋር ጮክ ብሎ መነጋገር አይፈቀድም፡፡ በሦስተኛው ቀን ሴቶች ቤቱን ያፀዳሉ፡ ወንዶች ደግሞ ከመስዋዕቱ የተረፈውን ምግብ ውሾች በልተው ቆሌውን እንዳያስቀይሙት ጉድጓድ ቆፍረው ይቀብሩታል፡፡ በመጨረሻም ግዴታ ባይሆንም እንደተለመደው እራሳቸውን ቅቤ ቀብተው የዕለት ተዕለት ተግባራቸውን ይቀጥላሉ፡፡

ጠባቂ ቆሌዎች የተለዩ ስሞች ቢኖራቸውም በጣም የታወቁት «ውቃቤ» እና «ተያዥ» የተባሉት ናቸው፡፡ ሁሉም

ሰዎች እንደሚተማመኑበትና እኔም ልዩነታቸውን ለማወቅ ባደረግኩት ጥረት ከስም ልዩነት በስተቀር ሁለቱም አንድ ዓይነት መናፍስት ናቸው። «ውቃቢ»፣ «ተያዥ» ሁለት የተለያዩ የአገው የግል ቆሌ የነበሩ ቢሆንም አሁን ግን ልዩነቱ ጠፍቶ ሁለቱም አንድ ሆነዋል። «ውቃቢ-ተያዥ» በአማራውና በፈላሻው የታወቀ ጠባቂ ቆሌ ነው። እንዲሁም ብዙ ኢትዮጵያውያን ከአረቡ ጂኒ መንፈስ ጋር ቢተዋወቁም በትግንቱ ኅብረተሰብ ዘንድ እምብዛም አልተለመደም።

አልፎ አልፎ የነቃ ጠባቂ መንፈስ አንድ ግለሰብን ሕመምተኛ በማድረግ ከቤቱ የአልጋ ቁራኛ ያደርገዋል። ይህ ዓይነት ሁኔታ በሚፈጠርበት ጊዜ ቃልቻው ለሥራው የሚያስፈልጉትን መሣሪያዎችና ቁሳቁሶች በመያዝ ወደ በሽተኛው ቤት ይሄዳል። እዮን ካጋጠሙት አንድ አስቸጋሪ ሕመምተኛ በትኩሳትና በቁርጥማት ካንድ ሳምንት በላይ ሲሰቃይ የቆዩ ሰው ነበር። በሽታው የመጣው በተያዡ ምክንያት ይሆናል በሚል ግምት የሰውየው ዘመዶች እዮን ጠሩት። እዮም ሕክምናውን ለማከናወን በሁለት ጊዜ ሊከፈል የሚገባውን ሁለት ብር ጠይቆ ቤተሰቦቹ ስለተስማሙ ሥራውን ቀጠለ።

በጭንቀት በተዋጡትና በሚያለቅሱት ቤተሰቦቹ መካከል እዮ በአንድ አርጩሜ ላይ ከበሽተኛው አልጋ አጠገብ ተቀምጦ ድቤውን መምታት ጀመረ። እዮ የዛሩን ዘፈን እየዘፈነና ወዲያና ወዲህ እየተወዛወዘ በጉንጩ ውስጥ ያጨቀውን ጫት እያመነዠከ እያለ ድንገት የዛር ዘፈኑን አቁሞ ለሃያ ደቂቃ ያህል ፀጥ ባለ የእንቅልፍ ሰመመን ውስጥ ገባ። እንደነቃ ከሰውየው ተያዥ ጋር እንደተነጋገረና የተያዥው ቅሬታና ቁጣ ጨርሶ በመዘንጋቱ መሆኑን አስረዳ። ውቃቢውን ለማለስለስ ማር፣ ጫት፣ እና ውሃ አንድ ላይ ተፈልቶ የሚጠጣውን «አውዛ» የተባለውን መጠጥ አጠጣው። ቀጥሎም ከአካባቢው የሚገኝ አንድ የጫካ ሥራ-ሥር ከውሃ ጋር አፍልተው እንዲሰጡት ትዕዛዝ ሰጥቶ መጠጡ የሚሰማውን ሕመም እንደሚያሻሽለው ገለፀ። እንዲሁም ሌላ ጫት ካኘከ በኋላ በሰውየው ፊት እትፍትፍ አለበት። ነገሩ ተያዡ እንዲያናግረው ነበር፤ ነገር ግን የታመመው ሰውዬ ፀጥ ብሎ አልጋው ላይ ለጥ ብሎ ቀረ። ድቤው ቢደለቅም ሆነ ዘፈኑ ቢሟሟቅ እዮ የሰውዬውን ውቃቢ መቆጣጠር አቃተው።

በመጨረሻም አዩ ተያዡን ሊሊት በንግግር ሊያግባባው ሙከራ አደረገ። ተያዡ ገበሬውን እንዳያስቸግረውና እሱም በአፀፋው በየጊዜው አዲስ ልብሶችን በመልበስ አሁንም ሆነ ወደፊት የዶሮ መስዋዕት እንደሚያደርግለትና ከዛር አለቃው ጋር ግንኙነት እንደሚያደርግ ቃል ገባ። አዩም ለሕመምተኛው ይህን ከፈፀምክ ውቃቢው ወደፊት ሌላ ችግር እንዲደርስበት አያደርግም፤ ነገር ግን በዓመት አንድ ጊዜ ሊመጣ ይችላል አለው። ከዚህ ላይ ሳልገልጽ የማላልፈው ነገር ቢኖር ሰውየው በሚቀጥለው ሳምንት ከሕመሙ እያገገመ ስለመጣ አዩ ስላዳነውና የመንፈስ እርጋታም ስላስገኘለት ከፍተኛ ምስጋና ማቅረቡን ነው።

አዩ ከሚጠቀምባቸው አንዳንድ መድኃኒቶች የበሽተኞችን ጭንቀት የሚያቃልሉ ከመሆኑም በላይ አንዳንዶቹ የሆድ መታወክ የመሳሰሉትን በሽታዎች ሲያስታግሱ፣ ሌሎች ግን ውጤታማ አይሆኑም። በቴክኖሎጂ ኋላቀር በመሆናቸው ስለበሽታ አመጣጥና ስለዘመናዊ ሕክምና ያላቸው ግንዛቤ ዝቅተኛ በመሆኑ አዩ በሚያደርገው ፈውስ ብዙ ጊዜ ይረካሉ። በሕመም ምክንያት በሚከሰት ችግር አንድ ነገር መደረግ ስላለበት አዩ ኃላፊነቱን ወስዶ ነገሮችን ለማስተካከል በጥቃቅኑ ነገር በምታስጨንቀውና ጠባይዋ በማይታወቀው የእነሱ በሆነችው ትንሿ ዓለም ውስጥ ጥረት ያደርጋል። ሃብታ በማትረባ ረገድ ባለው ኃይል ሁሉ እንደ የታመመ ሰው የአእምሮ ጤንነት እንዲያገኝና ተጨባጭ ለሆነው በሽታም ሆነ ረቂቅ ለሆነው መለኮታዊ በሽታ ፈውስ ለማግኘት ይጥራል። በሽተኛውን ለማዳን ካልቻለ አዩ በርካታ ምክንያቶች መስጠት ይችላል። «ሊታረቅ የማይችል ዛር ወይም በስህተት የተደረገ የቅዳሴ ሥርዓት» የመሳሰሉትን ምክንያቶች ይደረድራል። በዚህም ምክንያት አንድ ሰው በበሽታ ሲሞት ቅማንቶች የቃልቻውን ሕጋዊነት ወይም ስለሠራው ጥፋት አይጠይቁትም።

ልዩ የበሽታ መናፍስት። በቅማንት፣ በአማራና በፈላሻዎች ዘንድ አንድ ሰው በሌላ ሰው ካልተገደለ በስተቀር ሌላው ዓይነት ሕመምና ሞት ልዕለ-ፍጡራዊ (መለኮታዊ) በሆነ መናፍስት ወይም ውቃቢ ወይም በክፉ ዓይን ምክንያት የመጣ መቅሰፍት ነው ብለው የሚያምኑት።

የግል ቆሌዎች በአንድ ሰው ላይ ሕመም የሚያስከትሉ ቢሆንም የተለያዩ ቆሌዎች ደግሞ በጠቅላላው ለኅብረተሰቡ በሽታና ሕመም በወረርሽኝ ደረጃ ሊያመጡ ይችላሉ ይባላል:: እነዚህ መናፍስት ከዚህ በስተቀር ሌላ ተግባር እንደሌላቸው ነው የሚታወቀው::

በዚህ ዓይነት በሽታ የሚጠቁ ኅብረተሰቦች ተሰባስበው «በሽታውን ለመሸኘት» ረዥም የጉዞ ሥነሥርዓት ያደርጋሉ:: ይህ ጉዞ በኅብረተሰቡ ዘንድ ስለበሽታው ያለውን ጭንቀት ለመቀነስና ለማስወገድ አስጊውንና ገዳዩን በሽታ ያባረሩ እየመሰላቸው የሚወስዱት እርምጃ ነው:: ይህን ዓይነት ጉዞ በቤጌምድር ጠቅላይ ግዛት እ.ኤ.አ. 1964 ዓ.ም. የወባ ወረርሽኝ በሽታ ተነስቶ በነበረበት ጊዜ ለመታዘብ ችያለሁ:: ጉዞው የወባ ወረርሽኙ ቆሌው አስነስቷል ከተባለበት ከጐንደር ደቡባዊ ምሥራቅ በለሣ ከተባለ ቦታ ጀምሮ በሰቀልትና ጭልጋ አልፎ ሱዳን ጠረፍ ወደምትገኘው መተማ ነበር ያለፈው:: ብዛታቸው ሠላሣ የሚደርስ እያንዳንዱ ተጓዥ በሽታው አለበት የተባለውን ትንሽ ማሰሮ ወይም ቅምጫና (ቅል) አንጠልጥሎ ነበር:: አዲስ ቦታ ላይ ሲደርሱ እዚያው ላሉት ነዋሪዎች ማሰሮውንና ቅሉን ያስረክቡዋቸውና እነዚያም በተራቸው ሌላ ሥርዓተ ጉዞ በማድረግ ቅብብሉሽ ይቀጥላል:: የጉዞው ተካፋዮች እንደ መኖሪያ አካባቢያቸው አማራ፣ ቅማንትና ፈላሻዎች ነበሩ:: በሽታውን ያስከተለውን ቆሌ በሚገባ አርቀው ካልሸኙት ተመልሶ ያንሰራራል የሚል ስጋት ስላለ ሁሉም ኅብረተሰብ ከልቡ በመነሳሳት አሸኛኘቱን እስከ መጨረሻው ቦታ እስሚደርስ ኅብረተሰቡ ከአንዱ ወደ ሌላው ማሸጋገር የውዴታ ግዴታ ነበር::

ቅማንቶችም የፈንጣጣና የተስቦ ወረርሽኝ ሲፈነዳ መልሶ ለመከላከል የበሽታ አሸኛኘት ያደርጋሉ:: ጉዞው በሽታው ከተከሰተበት ቦታ ይነሣና ከዋና አውራ ጐዳና ላይ ሲደርስ አረፍ ብለው ስዎቹ ይዘው የመጡትን ምግብና መጠጥ ከበሉና ከጠጡ በኋላ በከፊል ምግቡንና መጠጡን በጥንቃቄ ለቆሌው በመተው ይመለሳሉ:: ቆሌውም ተመልሶ እንደማይመጣ ተስፋ ያደርጋሉ::

## ጥንቆላ፣ አስማትና ትንበያ

ቅማንት፣ ሌሎች አገዎችና አማራው ከአካባቢያቸው በተወረሱና በተለመዱ ጥንቆላ፣ አስማትና ትንበያ በተባሉት ሦስት

ልዕለ-ፍጡራዊ (መለኮታዊ) ችሎታዎች ያምናሉ፡ ተግባራዊም ያደርጋሉ፡፡ እነዚህ ከሰው ችሎታ በላይ የሆኑ ተግባሮች ማኅበራዊና ሥጋዊ ዓለማቸውን ለመቆጣጠር የሚያስችላቸውና ወደፊት የሚከተለውን አጋጣሚ ሁሉ ለማወቅ የሚረዳ ነው ብለው ያምናሉ፡፡ በተለይ ቅማንቶች አንዳንድ ችግሮች አብጠው ከመፈንዳታቸውና ኀብረተሰባቸው ላይ ጥላቻና ግጭት ከመፈጠሩ በፊት እነዚህን ሦስቱን ተግባሮች የችግሮች ማስተንፈሻ ያደርጓቸዋል፡፡ ለምሳሌ አንድ ገበሬ ቀጥታ ባለ አንግጣውን ሄዶ ከመደብደብ ይልቅ በምሥጢር በሰብሉም ሆነ በቤተሰቡ ላይ መጥፎ አጋጣሚ እንዲደርስበት ከተራገመ ወይም ከተሳለ አስቸኳይ የሚያረካው እርምጃ እንደወሰደ ይቆጥረዋል፡፡

ጥንቆላ በሰዎች አእምሮ ላይ ክፋት ማድረስ የሚያስችል በግለሰብ ውስጥ ያለ ኃይል ነው፡፡ ጠንቋዮች ብዙ ጊዜ ሴቶች ቢሆኑም ወንዶችም አልፎ አልፎ አሉበት፡፡ ጥንቆላ ከተፈጥሮ የሚመነጭ ኃይል ቢሆንም ችሎታው የተደበቀና ያደፈጠ፡ አልፎ አልፎ የሚከሰት ነው፡፡ ይህ ዓይነት ችሎታ ያለው ሰው ምንም እንደሌለበት የማያውቅበት ሁኔታም አለ፡፡ እንደነዚህ ያሉ ሰዎች የክፋት ወጥመዳቸውን እስከሩቅ ቦታ መዘርጋት ይችላሉ፣ ወደተለያዩ እንስሳት መለዋወጥ ችሎታው አላቸው፡ እንዲሁም በአንድ ጊዜ እይታ (ዓይን በመውጋት) ወይም በንግግር (ምላስ) ብቻ አንድን ነገር ማጧጧት የሚችሉ ናቸው፡፡ ጥንቆላ ያልታሰቡ አጋጣሚዎችን በተጨባጭ ለማስረዳትና ለማብራራት የማይቻለውን ለማወቅ የሚረዳ ነው፡፡ በጥንቆላ የተደረጉ ወንጀሎችም ለመኖራቸው አንዳንድ ማስረጃዎች ይጠቁማሉ፡፡

«አስማት» እንደ ጥንቆላ ውስጠ-በቀልና አብሮ-አደግ አይደለም፡፡ አካባቢውን በመቆጣጠር ለተፈለገው ማኀበራዊና ምድራዊ ዓለም ለማዋል በማቀድ አስቀድሞ በተጠና ስልት አንዳንዴም በሚያፈዝ መድኃኒት በመጠቀም በማደንዘዝና ልዩ ቁሳቁሶችን ለዚህ ተግባር በማዋል የሚደረግ ነው፡፡ የእነሱ አስማት ለክፋም ለደጉም ሊዳርግ የሚችል ሲሆን በምዕራባዊ ዓለም ካለው በእጅ ቅልጥፍና ሕዝብን ለማዝናናት ከሚደረገው አስማት የተለየ ነው፡፡ ቢሆንም ማንኛውም የሃይማኖት ሰው የእጅ ቅልጥፍናን በመጠቀምም ሆነ በመንፈስ በመያዝ ሊገባን በማይችል ቋንቋ በሚያደርጉት ድግምት ሊያደናግሩን ይችላሉ፡፡

«ትንበያ» ደግሞ ወደፊት ምን ሊሆን እንደሚችል ለማወቅ የሚያስችል ልዕለ-ፍጡራዊ ችሎታ ነው:: ሁለት ዓይነት ትንበያዎች አሉ:: አንዱ በቃልቻ አማካይነት ከመናፍስት ስሚት የሚገኝ፣ ሌላው ደግሞ ወደፊት ሊከሰቱ የሚችሉትን ምልክቶች በመመልከት የጥንቆላ ስልትን በመጠቀም ትርጉም መስጠትን የሚያጠቃልለው ነው::

ቃልቻነት፣ ቀሳውስት በሃይማኖት ውስጥ ያላቸው የሥራ ድርሻና በዚህ ርዕስ የተገለፁት ሦስቱ ልዕለ-ፍጡራዊ ችሎታዎች እያንዳንዳቸው ተነጣጥለው ራሳቸውን ችለው የሚታዩ አይደለም:: የተለያዩ ተግባሮችንም ሲያከናውኑ ይህን ያህል ግልጽ የሆነ አንዱን ከሌላው የሚለየው ነገር የለም:: ብዙ ደብተራዎችና (የቅማንት ቀሳውስትን አይጨምርም) ቃልቻዎች የጥንቆላ፣ የአስማትና የትንበያ ሥራ እየሠሩ በሌላ በኩል ደግሞ ጠንቋዮች በተጨማሪ የትንበያ ወይም የአስማት ሥራ ሲሠሩ ይገኛሉ:: እንዲሁም አንድ አስማተኛ ጠንቋይ ወይም ተንባይ ሆኖ የሚገኝበት ጊዜ አለ::

ጠንቋይ ፍለጋ:: በቅማንት አካባቢ ጠንቋይ ማግኘት አስቸጋሪ ነው:: ቅማንትም ሆነ የሌላ የጐሣ አባል ቃልቻ ወይም አስማተኛ ወይም ተንባይ የሆነው ሁሉ የጥንቆላ ሥራ እየሞከረ ጠንቋይ ነኝ ካለ ሕዝቡ ጠንቋይነቱን ይቀበላል:: በሰዎች፣ በእንስሳትና በሰብል ላይ የመጠውለግ ሁኔታ ሲያጋጥም፣ ምንም እንኳን ሰዎች ጠንቋይ ነን ብለው ባያምኑም፣ አንዳንዶቹን በጠንቋይነት ይጠረጥሩአቸዋል:: በኑሮአቸው ላይ አንድ ችግር ሲፈጠር በእራሳቸው አርቆ አስተዋይነት ድክመት ምክንያት ለሚደርሱ ችግሮች ሁሉ ጠንቋይ ናቸው ብሉ በሚጠረጥሩአቸው ላይ ችግሩን ይላክኩባቸዋል:: ከሩቅ ቦታ የሚኖር አንድ ኅብረተሰብ አባል ወይም ጉረቤት የሆነ በማያውቀውና ሌላ ሰው በአደረሰው መጥፎ ድርጊት በጠንቋይነት ሊወነጀል ይችላል::

ቅማንቶችና ጉረቤቶቻቸዉ «ኃይለኛ ዓይን»፣ «መጥፎ ምላስና» «ክፉ ሃሳብ» እንዳሉ ያምናሉ:: እነዚህ ሦስቱ ነገሮች በቅማንት ከታወቁት የጥንቆላ ሥራዎች ዋናዎቹ ሲሆኑ አገውና አማራም ብዙ ጊዜ ተንኮለኞች በምቀኝነትና በቅናት በመነሣሳት ይህንን ዓይነት ተግባር ይፈጽማሉ ይላሉ:: በአንድ ግለሰብ ንብረት ላይ በስስት ዓይን አተኩሮ በማየት ድህነትን ካስከተለበት ይህን

ያደረገው የ«ቡዳ» ዓይን አለው ይባላል። ማንኛውም ሰው ከማንኛውም ጐሣ ቢሆን «ቡዳ» የሚለው ስያሜ ሊሰጠው ይችላል፣ ብዙውን ጊዜ ግን አንዱ በሌላው ጐሣ ላይ ቡዳነትን ይላክካል። አብዛኛው አማራ ፈላሻውን ቡዳ ነው ሲል ጥቂቶቹ ቅማንት ነው ይላሉ፣ ቅማንቱ ደግሞ ፈላሻው ነው ቡዳ ማለት የተለመደ ነው። በሌሎች ጐሣዎች በቡዳ እንዳይያዙ በማሰብ ቅማንቶች ራሳቸውን አግልለው ግንኙነታቸውን የሚያጠናክሩት እርስ በእርሳቸው ነው።

አንዱ ጐሣ በሌላው ጐሣ ከጥንቆላ ጋር በተያያዘ ምክንያት ስለሚነሳው ፍራቻና አለመተማመን እንዳለ አንድ ቀን ከአማራውና ከቅማንት ድንበር አጠገብ በሚገኝ አንድ የፈላሻ ሠፈር ጠፍቼ ያጋጠመኝን ላውራችሁ። የምሄድበት መንገድ ጠፍቶብኝ ስማስን ሁለት ፈላሻዎች አገኘሁና መንገድ እንዲያሳዩኝ ጠይቂያቸው ትንሽ ጋራውን ካሳለፉኝ በኋላ ከእንግዲህ አንቀጥልም በማለት አሻፈረን አሉ። ለማሳመን ከብዙ ክርክር በኋላ አንድ ብር ስጥቻቸው ሊያደርሱኝ ተስማምተው ትንሽ ተጉዘን የፈላሻውን መሬት አልፈን ከአማራውና ከቅማንቱ መሬት ድንበር ላይ ደረስን። ከዚያ በኋላ ግን አስር ብር እንኳን ብጨምርላቸው በምንም ዓይነት እንደማይንቀሳቀሱ ወሰኑ። ነገሩ ወዲያውኑ ገባኝ፤ ይኸውም ፈላሻዎች ድንበሩን አልፈው ከሄዱ አማራውም ሆነ ቅማንቱ አስከሬን አውጥተው ለመብላት ወይም በአንዱ ላይ የጥንቆላ ሥራ ሊሠሩ የመጡ ወይም ቡዳ ናቸው ተብለው በመወንጀል መዓቱን ያወርዱብናል ብለው በመፍራታቸው ነበር። እኔም የመንገድ መሪዎቼን አጥቼ በጭለማ እየተደናበርኩ ወደ ሠፈሬ መንገዴን ቀጠልኩ።

ማርቲን ፍላድ የተባለ በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የነበረ ሚስዮናዊ በምግብና በዓይን ስለነበረው አስተሳሰብ የታዘበው ሁኔታ እስካሁንም አለ። ፍላድ እንደገለጸው ማንኛዋም ሴት በምታዘጋው ምግብ ላይ የእንግዳ ክፉ ዓይን እንዳያርፍበት ማጀት ውስጥ ደብቃ ነው የምትሠራው። ይህንንም ፍላድ ሲያጠናክር፦

«ሐበሾች (አማራና አገው) ክፉ የሰው ዓይን እንዳያጠላበት ምግብና መድኃኒት ሸፍነው መሄድ አለባቸው። ምግባቸውን የሚመገቡት በግለኛነትና ጨለማ እንኳን ቢሆን በበራቸው ላይ መጋረጃ አድርገው ሲሆን በምግብ ሰዓት ድንገት አንድ ሰው ዘው ብሎ ቤት ውስጥ ቢገባ ትህትና የጐደለው ይቅርታ የማይደረግለት

ድርጊት ሆኖ ነው የሚቆጠረው፡፡ ይላል፡፡ በዚህ ጉዳይ ላይ በምስራቅ አንድ ወደ ኢትዮጵያ የመጡት የውጭ አገር ጉብኚዎች እንደዘገቡት የኢትዮጵያ ባህል እየተለወጠ ነው ወይስ እንዳለ ሳይነካ ቆይቷል የሚለውን ጥያቄ ለመመለስና ለመገምገም ያስችለናል፡፡

በኅብረተሰቡ ዘንድ የታመነውና ማንም ሰው ሊያደርገው የሚችለው ሌላው ነገር ደግሞ አንድን ሰው ወይም ዕቃ ትኩር ብሎ በቅናት በማየት ክፋት በማድረስ የታወቀው «ዓይን መውጋት» የተባለው ነው፡፡ በቅማንት አካባቢና በጉርብትና የሚኖረው ሕዝብ እንደአስማተኛ ዓይን መውጋት ይችላል ይባላል፡፡ ሁለተኛው ዓይነት ልዕለ-ፍጡር ኃይል ደግሞ «ጥቁር ምላስ» የሚሉት ነው፡፡ ይህም የሚደረገው አንድን ሰው ወይም አካል ትኩር ብሎ በመመልከትና ድምጹን ከፍ አድርጎ አጋንኖ ማድነቅ ሲሆን ድርጊቱ የተፈፀመበት ሰው የአካል መመናመን ያስከትልበታል ይባላል፡፡ ሦስተኛው ደግሞ «ስም ማንሳት» ወይም ስለአንድ ግለሰብ መጥፎ መመኘት ነው፡፡ ኅብረተሰቡ ውስጥ ችግር ፈጣሪና አዋኪ ሰው ካለ ሕብረተሰቡ «ይጣለው» ብሎ የሚያውግዘው አንደኛው ዓይነት ስም ማንሳት ነው፡፡ «ስም ማንሳት» ከሌላው ምትሀት ሁሉ በግልጽ የሚደረግ ስለሆነ የሚረገመው ሰው መንፈሱ በመረበሽ ይታመማል፡ በመጨረሻም ሊሞት ይችላል፡፡ በዚህ ሁኔታ የሞተን ሰው ሕብረተሰቡ «ስም ማንሳት» ገደለው ነው የሚሉት፡፡

ድግምት፡፡ በቅማንት አገር አስማት በቃልቻዎች፣ እውቀቱ ባላቸው የማንኛውም የጐሣ አባል፣ በደብተራዎችና በፉቅራዎች ይከናወናል፡፡ ብዙ ጊዜ በጐ የሆነ አስማት ክፋውን አስማት ለመከላከል የሚደረግ ነው፡፡ ለበጐ ነገር የሚደረግ አስማት ከዓይን-ወጊ (ጥላ ወጊ) ለመዳን ታስቦ የሚደረግ ነው፡፡ እንስሳትን ከዓይን-ወጊ ለመጠበቅ የጥጃዎች ጆሮ ጫፍ ተቀርጥፎ ይጣላል፡ አዝመራን ከክፉ ዓይን ለማትረፍ የከብት ቀንድ በእንጨት ላይ ተሰክቶ ወይም ቅርፊታቸው የተላጠ የዛፍ ቅርንጫፎችና አጣናዎች ከሰብሉ መሃል ላይ ቀጥ ብለው ይተከላሉ፡፡ ለምን እንደሚደረግ ምክንያት ሊሰጥ ባይቻልም «ስለፍቱንነታቸው እርግጠኛ ነው» የሚለው መልስ ግን አለ፡፡

እራስን ከክፉ አስማትና መጥፎ መናፍስት ተንኮል ለመጠበቅ ቅማንት፣ ፈላሻና አማራ እንደጌጥ እንዲያገለግል ሆኖ በትንሽ ቆዳ የተለበደ ክታብ ከአንገታቸው አጥልቀው ይሄዳሉ። በክታቡ ውስጥ በግዕዝ ወይም በአረብኛ ወይም ሁለቱ የተቀላቀሉበት ከመጽሐፍ ቅዱስ ወይም ከቁርዓን የተወሰዱ በብራና ላይ የተጻፉ ጥቅሶች ይኖሩአቸዋል። ሁረያውን ምስሎችና የጌጥ ዲዛይኖች ይታከላሉ። የተጻፉት ቃላት ክፉውን የሚከላከለ ብቻ ሳይሆን የኢትዮጵያ ገጠሬ መሃይም በመሆኑ እራሱ ጽሑፍን እንደ ድግምት ነው የሚቆጥሩት። ከነዚህ ክታቦች በስተቀር ሌሎች በአንገት ላይ የሚደረግ ሰው ሰራሽ ጌጣጌጥ ቅማንቶች አያደርጉም። ተንኮለኛ አስማተኞች እኩይ ተግባራቸውን በልምድ ተገኙ መድኃኒት በአካል ላይ ጉዳት የሚያደርሱ ድርጊቶችን ይፈጽማሉ። በበለጠ ግን በድግምታቸውና በሚተምሙት መድኃኒት በመተማመን በግለሰቦች ላይ የሚፈጽሙት መሠሪነት ነው። ይህ የተንኮል ድርጊት በአቶ ረዳ ላይ ደርሶባቸዋል። ይኸውም መጥፎ እድል እንዲደርስባቸው ያሰበው ጠላታቸው የበሰበሰና «የተደገመበት» እንቁላል ከጠንቋይ ላይ ይገዛና በማግስቱ ጨለማን ተገን በማድረግ ውሾቹ መተኛታቸውን አረጋግጦ እንቁላሎቹን ቤታቸው አጠገብ ቀብሮ ይሄዳል። ነገር ግን ሚት አቶ ረዳ አዲስ ምልስ አፈር በማየታቸው በነገፋ ነትተው ወዲያውኑ እንቁላሎቹን ቆፍረው በማውጣት ማስረጃዎቻቸውን በመያዝ ለሽማግሌዎች በማቅረብ ያልታወቀው ጠላታቸው እንዲረገም በአንክሮ ለሽማግሌዎች ጥያቄያቸውን አቀረቡ።

አቶ ረዳ እኩይ የሆነውን ተግባር እንደሌሎች የአስማት ሥራ ሁሉ አደገኛ መሆኑን ስለሚያውቁ እንዲህ መረበሻቸው አለነገራቸው አልነበረም። አንድ ሰው በአደባባይ ላይ ከተረገመ ወይም ድግመት ከተደረገበት መጥፎ እድል የሚያስከትል ከመሆኑም በላይ ሰዎች በጣም እንደሚታመሙና በሕመሙም እንደሚሰቃዩ አቶ ረዳ በዓይናቸው ያዩት ነገር ነበር። በድግምት የሚያምን አንድ ሰው የአእምሮና የሰውነት ሕመም ሊሰማው ይችላል። ይህንን ክስተት በተለይም ለሞት ከበቃ «በአስማት ሞተ።» ይባላል። በአስማት ማመን በግለሰቦች ላይ በምንም ዓይነት ሰውነት ሊቆጣጠረው የማይችል ፍርሃት ያስከትላል፣ የሰውነቱ የመከላከል ዝግጁነት በድንጋጤ ጨርሶ እስከሚዋጥ ይቆይና ወዲያውኑ ለመኖር መሠረታዊ የሆኑት ምግብና ውሃ

ያስጠሉታል፡፡ አቶ ረዳ እንደዚህ ዓይነት የአእምሮና የመንፈስ ጭንቀት ከስተት መኖሩን ባያውቁም በእሳቸው አመለካከት አስማትና ጥንቆላ እንዲሉና በጣም አደገኛና ድራሽ የሚያጠፉ መሆኑን ይገነዘባሉ፡፡

አቶ ረዳ ጉዳዩን ለማስተካከል እንደአመጣጡ የወሰዱት እርምጃ አግባብ ነው ብለው ያምናሉ፡፡ የቴክኖሎጂና የሳይንስ እውቀት በማይታወቅበትና የባህል እድገትም ባልዳበረበት ሁኔታ ግለሰቡ በደረሰባቸው አሳዛኝ ሁኔታ በራሳቸው እምነት የወሰዱት አቋምና ሊያደርጉት ያሰቡት ትክክለኛ ነው ሊያሰኝ ይችላል፡፡ አቶ ረዳ እንስራ ሲፈልጉ ወደ ሸክላ ሰሪ፣ የብረት መሳሪያ ከተበላሸ ወደ ብረት ቀጥቃጭ፣ ከጠንቋይ ለሚመጣ ድግምት ወደ ሙያተኛው እንደሚሄዱ ሁሉ ስለተቀበረው የእንቁላል ምስጢር ወደ ቃልቻ መሄድ ነበረባቸው፡፡ እድለኛ ሆነው ታናሽ ወንድማቸው አየ ቃልቻ ስለሆነ ተደግሞበት ለተንኮል ስለተቀበረው እንቁላል አፍራሹን (ማርከሻውን) ድግምት በአነስተኛና ለምልክት ያህል በሚከፈል ዋጋ መፍትሄ እንዲፈልግላቸው ተደረገ፡፡ በአየ በኩል መደረግ የነበረበት አቶ ረዳ ስለ እንቁላሉ በአእምሮአቸው የተቀረፀውን መጥፎ ስሜት ማስወገድ ነበር፡፡ ይህ በእዚህ እንዳለ የሽማግሌዎች ሸንጎ በአቶ ረዳ ላይ ተንኮሉን ፈጽሟል ተብሎ ስለተጠረጠረው ሰው ተጨባጭና አሳማኝ ማስረጃ እስከሚገኝ እርግማን የማሳለፉን ጉዳይ አዘገዩት፡፡ መሠረው፣ የሽማግሌዎቹን እርግማን በመፍራትም ይሁን ወይም የቃልቻውን የአየን አስማት ኃይልነት በማወቅ ሊሆን ይችላል፣ በድጋሚ ተንኮሉን ከመፈፀም ታቀበ፡፡

የነገን ባሬ መተንበይ፡፡ እንደማንኛውም ሰው ቅማንቶች «ነገ» ምን ይዞ እንደሚመጣ ለማወቅ ይጓጓሉ፡፡ ስለዚህም ስለወደፊቱ የሕይወት ከፍና ዝቅ ማለት አንዳንድ መረጃዎችን ማግኘት ይፈልጋሉ፡፡ ይህን መረጃ ለማግኘት ግለሰቦችና የሃይማኖት ሰዎች ትንበያን ይሞክራሉ፡፡ ሊከሰቱ የሚችሉትን ሁኔታዎች ከተንባዮች በመረዳት ስጋታቸው በመጠኑም ቢሆን ስለሚቀንስላቸው በዚች ምድራዊ ዓለም አስተማማኝና የተረጋጋ ማኅበራዊና ባህላዊ ኑሮአቸውን ለመምራት ይረዳቸዋል፡፡

የአቶ ረዳ ልጅ ቢተው ከኅብረተሰቡ ወጣ ወዳለ ቦታ ለመሄድ መንገድ ሲጀምር አንዳንድ የግለሰብ ስሞችን ይሰማል፡፡

ሰሞቹ በደስታ፣ በሀብትና በብርሃን የሚመስሉ ከሆነ ጥሩ እድል የሚያጋጥመው ስኬታማና አስተማማኝ ጉዞ እንደሚሆንለት፣ ነገር ግን «ስበር»፣ «ዝረፍ»፣ «ኃይለኛው»፣ «ያዘው» የሚባሉ ስም ያላቸው ሰዎች ሲያጋጥመው ደግሞ መጥፎ ዕድል ያጋጥመኛል ብሎ ስለሚያምን ጉዞውን ሠርዞ ወደ ቤቱ ይመለሳል:: በሌላ በኩል ወንድሙ ነጋሽ ይህን በመሳሰሉ መልክቶች እንደ ቢተው ስለማያምን ከፍ ብሎ የተጠቀሱት ስሞች ቢያጋጥሙት በምንም ዓይነት ከጉዞው አይደናቀፍም:: ቢሆንም ነጋሽ በመንገድ ሲሄድ ሁለት ሰዎች ሲያጋጥሙት ወይም ሙሉ የሆነ እንስራ ወይም ስልቻ የተሸከመ አንድ ሰው በመንገድ ላይ ቢያገኝ እንደ ጥሩ እድል ይቆጥረዋል:: ባዶ ዕቃ የተሸከመ ሰው ካጋጠመ በጣም መጥፎ ዕድል ያጋጥማል ተብሎ ነው የሚታመነው::

በቅማንት አገር አንደንድ ሰዎች ከአብዛኛው ኅብረተሰብ ስለ ትንበያ በተሻለ ሁኔታ የሚያውቁ አሉ:: ቃልቻዎች በዛር አማካይነት ወደፊት የሚሆነውን ነገር ይተነብያሉ ወይም ደግሞ የተደበቀ መረጃን ከተደበቀበት ቦታ ያገኛሉ:: ሌሎች ብቸኛ የሆኑ ተንባዮች ሲሆኑ የወፍ ቋንቋ እናውቃለን እያሉ የወፎችን የበረራ አቅጣጫ በመመልከት ወደፊት ምን እንደሚመጣና እንደሚፈጠር ይጠቁማሉ::

ከአዮ ጋር የምትፎካከር አንዲት የሴት ጠንቋይ ነበረች:: የእሷን ችሎታ ለመፈተን ሲል አንድ የመንግሥት ሹም ከአሽከሮቹ አንድ ጠብመንጃ ወስዶ ስውር ቦታ ይደብቅና ጠብመንጃው የት እንዳለ ጠንቋይዋን ጠይቋት ይላቸዋል:. አሽከሮቹም እንደተባለው ሲጠይቋት በትክክል መሣሪያው የት እንደተደበቀ ነገረቻቸው:: በዚህም ምክንያት በችሎታዋ የተደነቀው አውራጃ ገዥ ጠብመንጃውን እንደሸለማት በቅማንት አገር በብዙ ሰዎች እንደትንግርት ይነገርላታል::

ይህንን ምዕራፍ ለመቋጨት አንድ የኅብረተሰብ ማኅበራዊ ማስታወሻ እተዋለሁ:: ከአንድ በኢንዱስትሪ የበለፀገና የተማረ ሕዝብ ከሚኖርበት ምዕራባዊ አገር አንዳንድ ሥራዎችን ለመሥራት ወደ ኢትዮጵያ የመጣ ሚሲዮናዊ ጋር ስንነጋገር፣ «የሰሜን ማዕከላዊ የኢትዮጵያ ሕዝቦች ዛር ተሳፍሮብናል የሚሉት የተሳሳተ ነገር ነው፣ ይልቅስ በእነዚህ ምስኪን ሰዎች ላይ የተሳፈረባቸው ዛር ሳይሆን ሠይጣን ነው» በማለት በአንክሮ

የነገረኝ ያስደንቀኛል። እስካሁን ድረስ ይህ ሚሲዮናዊ ሠይጣን ይዞአቸዋል ያላቸውን ሰዎች ሠይጣኑን ከሰውነታቸው ለማስወገድ ያለመታከት ጥረት እያደረገ ነው። በዚህ አርእስት ስለ ልዕለ-ፍጡራዊ ክስተቶች ስዕላዊ በሆነ መልኩ በአጭሩ ያየነው እዚህ ላይ ይብቃ። የምዕራቡ ዓለም አንባቢም አንዳንዶቹ የቅማንት ባህሎች ከራሱ ጋር ተመሳሳይና ብዙም የማይራራቁ መሆኑን ስለሚገነዘብ እራሱን በቅማንቶች ቦታ በማስቀመጥ የስሜታቸው ተካፋይ እንደሚሆን አልጠራጠርም።





# ምዕራፍ ስድስት

## የፖለቲካ አደረጃጀት

በጥንት ዘመን በተለይ በጦርነት ወቅት ወይም በኅብረተሰቡ ዘንድ ጠቅላላ ቀውስ ሲፈጠር የመጨረሻው የፖለቲካ ሥልጣን ለእያንዳንዱ የጐሣ አባት ለምሳሌም እንደ ዘጠኙ ቃሉት የ«ከብር» የባህል ጀግኖች ይሰጥ ነበር። (ቻርት ቁ.1 ይመልከቱ) በሠላም ጊዜ ግን ሥልጣን ዲሞክራሲያዊ በሆነ መንገድ ይከፋፈል ነበር። እ.ኤ.አ ከ1600 ዓ.ም. ትንሽ ቀደም ብሎ ቅማንቶች በፖለቲካው ረገድ በባላባታዊው አገዛዝ ሥር ቢወድቁም ምንም ብዙ የሚያስፈራ የጦር ኃይል ስላልነበራቸው ተፅዕኖ ሳይደረግባቸው የውስጥ የራስ ገዝ ሥልጣን ይዘው እንዲቆዩ ተፈቀደላቸው። የኢትዮጵያ ነገሥታት ዜና መዋዕሎች እንደሚያስረዱት ቅማንት ምንጊዜም በአማራው ላይ እንዳልተነሣና የእራሳቸው አፈ-ታሪክም ቢሆን የጦር ጀግኖቻቸው በአማራው መንግሥት ውስጥ ይሠሩ እንደነበር ነው የሚዘክሩት።

ይህ ለረዥም ዘመን የቆየው ከፊል ነፃ የፖለቲካ አስተዳደር ተቋም ብዙ የፍትሕ አመራር ሥልጣንን ስላጐናፀፋቸው ከባህላዊ ሕጋቸው ያፈነገጠውን እንዲታረም በማድረግ እንዲጓዙ ረድቷቸዋል። በዚህም ምክንያት የጐሣው ማንነትና የኅብረተሰቡ አንድነት ለዘመናት ተጠብቆ ቆይቶአል። በ1880ዎቹ ቅማንት የአማራን ባህል እንዲቀበል ሲገደድ የቅማንት ሃይማኖት እየተዳከመ በመምጣቱና ባህላቸውና ፖለቲካውም በአንድ ላይ የተሳሰሩ ስለነበር ጥንታዊው የፖለቲካ መዋቅር ጭምር እንዳልነበረ ሆነ። የአንድነት መለያ የነበረው ተገልሎ የመኖር ስሜት እየተዳከመ መጣ። ምንም እንኳን የነገሥታቱ የማስገደጃ ትዕዛዝ ባይኖርም የአማራን ባህል የመቀበሉ ሂደት በፍጥነት ቀጥሎ ብዙዎች በባህል ለውጥ አማራ (አምሃራይዝድ) ሆኑ፡ ሂደቱም ቀጠለ።

አማራው በቅማንቱ ላይ የበላይነት ከያዘ ወዲህ የአስተዳደር ሥልጣን ደረጃው በየዘመናቱ የተለያየ ቢሆንም በአንፃሩ የባላባታዊ ሥርዓት ከመተከሉ በፊት የነበረውን ተመጣጣኝ የሆነ ሥልጣን እንዲያዙ ቆይተዋል። አማራው የፖለቲካውን ሥልጣን ቢይዝም፡ ፍትሕ አሰጣጥን በተመለከተ ቅማንቶች ከፍተኛ የውስጥ

ነፃነት ነበራቸው። ይህ ነፃነት በአማራው ላይ ምንም ሥጋት ባለማስከተሉ ቅማንቶች የእራሳቸውን ሕጋዊ ችግሮች በራሳቸው የፖለቲካና ሃይማኖታዊ አደረጃጀት ስልትና ሥርዓት መሠረት መፍትሔዎችን ያስገኙ ነበር። ሆኖም ከፍትሕ አሰጣጥ በስተቀር ሌላው ዓይነት ሥልጣን እስከ ተወሰነ ደረጃ ድረስ ነበር።

እንደጥንታዊው ዘመን ባህላቸው ቅማንት ዲሞክራሲያዊ ፈለግን በተከተለ መልክ ሥልጣንን ወደታች በተወረድ ያከፋፍሉ ነበር። በዚህም መሠረት አብዛኛው የአስተዳደርና የዳኝነት ሥራ የሚሠራው በመጨረሻው ዝቅተኛ እርከን ላይ በሚገኘው የአዛውንቶች ሸንጎ ሲሆን በዚህ ደረጃ ሊፈቱ ያልቻሉ የአስተዳደርና የዳኝነት ችግሮች በመካከለኛ ደረጃ ከዚህ በላይ ለሚገኙ ቀሳውስትና የታወቁ ግለሰቦች ላሉበት የፖለቲካ ሥልጣን ለያዘ ቡድን ይተላለፋል። በዚህ ደረጃ ችግሩ ካልተፈታ ደግሞ የመጨረሻውን የፖለቲካና የሃይማኖት ሥልጣን ለያዙት ለሁለቱ የዋልጋና የከርከር ወምበሮች ይተው ነበር።

## የአዛውንቶች ሸንጎ

የአዛውንቶች ሸንጎ መሠረታዊ የሆነ የቅማንት የሥልጣን ንዑስ ዘርፍ ነው። የአዛውንቶች ሸንጎ አባላት የሽማግሌዎችና በኅብረተሰቡ ዘንድ ተቀባይነትና አክብሮት ያላቸው ሰዎች ስብስብ ነው። ከፍተኛውን የመናገር፣ የመከራከርና የመወሰን የኃይል ሚዛን ያላቸው በ«ካማ» ሥነሥርዓት ያለፉ ማለትም ከጉልማሳነት ወደ አዛውንትነት በሥርዓት ለማለፍ መስፈርቱን አሟልተው አክብሮት የተሰጣቸው ብቱ ሽማግሌዎች ናቸው። ዋናው የደረጃቸው መለኪያ ወደ እግዚአብሔር (ምዝግና) የቀረቡ ናቸው ተብለው ሲታመን ነው። ሁሉም አዛውንቶች በ«ካማ» ማለፍ ባይኖርባቸውም የአዛውንቶች ሸንጎ ከሃይማኖት ጋር የተሳሰረ ነው።

ማኅበራዊ ኑሮን የሚመለከቱ፣ የአስተዳደርና የፍትህ የዕለት ተዕለት ጉዳዮች ለአማራው ባለሥልጣን ሳይተላለፉ ለቅማንቶች የአዛውንቶች ሸንጎ ተርበው ይወስናሉ። በዚህም ምክንያት የቅማንት ኅብረተሰብ በፍቅር ተሳስሮ እንዲኖር አጋዥ ሆኗል። ጥንት የከብር ዘር ያላቸው የሸንጉ አባላት አስተያየት ነበር ተሰሚነት የነበረው። ይህ ዓይነት ዝንባሌ በመስፈኑና የቀሳውስትና የወምበሮች ምርጫ ከቂስ ቤተሰብ ብቻ በመሆኑ

ከሞላ ጎደል ዴሞክራሲያዊ የነበረው ሥርዓት ወደ አንድ ቡድን አመራር ተለውጦ እንደነበር እንገነዘባለን። ሆኖም ባለፉት አርባ ዓመታት የ«ክብር» ዘር አባላት የበላይነት እየጠፋ በመምጣቱ የቡድናዊ አመራር ሥርዓትም ጉልቶ መታየቱን አቆመ።

መደበኛና መደበኛ ያልሆኑ ሸንጎዎች። ሁለት ዓይነት ሸንጎዎች አሉ፦ መደበኛና መደበኛ ያልሆኑ ሸንጎዎች። መደበኛ ሸንጎዎች ወርሃዊ ስብሰባቸውን የሚያካሂዱት የቅማንት ኅብረተሰብ በሚካፈሉበት ማሕበር ነው። (ስለ ማኅበራዊ አባልነት፣ አመራረጥና ዓላማ በሚቀጥለው ሰባተኛው ምዕራፍ ላይ ተገልጿል።) በመደበኛው ሸንጎ አዛውንቶች የፍትህንና የአስተዳደር ጉዳዮችን ለውይይትና ለውሳኔ ያቀርባሉ። በየዓመቱ የሚመረጥ መሪ (አለቃ) ስብሰባውን የሚመራ ሲሆን ለሚሰጠው አገልግሎት የሚከፈለው ነገር ባይኖርም በኅብረተሰቡ ዘንድ የተለየ ክብር ይኖረዋል። እንዳአስፈላጊነቱ አቤቱታዎችንና ክሶችን እያየ ከሸማግሌዎች መካከል መርጦ ላቋቋማቸው ንዑስ ኮሚቴዎች ሥራውን ያከፋፍላል። አንድ ንዑስ ኮሚቴ አንድ መሪና ሌሎች አምስት አባላት ያሉት ሲሆን ይህም እያንዳንዱ ወንድ ቅማንት በኅብረተሰቡ ውስጥ ባለው መንግሥት በሕይወቱ አንድ ጊዜ ሚና ኖሮት እንዲያገለግል እድል ያገኛል ማለት ነው። ንዑስ ኮሚቴው ጉዳዮቹን በማጣራት የመደበኛው ሸንጎ ውሳኔ እንዲሰጥበት ያቀርባል።

መደበኛ ያልሆኑት የአዛውንቶች ሸንጎዎች ከዚያም ከዚህም የተውጣጡና በከሳሽና በተከሳሽ የተመረጡ አንድ የቡድን መሪና ከአምስት እስከ ሰባት የሚደርሱ አባላት ያሉት ሆኖ ዋናው ሥራው የፍትሕን ሥራ ማከናወን ነው።

በመደበኛውና በንዑስ ሸንጎው፣ እንዲሁም መደበኛ ባልሆነው ሸንጎ የሚደረጉት ምርመራዎችና በጉዳዩ ላይ የሚደረጉት ውይይቶች ብዙ ወራትንና ከዚያም አልፎ ዓመታትን ሊፈጁ ይችላሉ። ይህም የጊዜ መራዘም በማኅበረሰቡ መረጋጋትን ያስከትላል፥ ምክንያቱም አንድ ቀን ተከራካሪዎቹ ሸንጎው በነፃ ይለቀናል የሚል ግምት ስለሚኖራቸው አንዱ በአንዱ ላይ ግጭት ለማስነሣት አይደፍርም።

ነስ። እድሜያቸው የገፋና በነግ ሥርዓት ያለፉ በመሆናቸው አቶ ረዳ የአንድ መደበኛ ሸንጎ አባል ሆነው አብዛኛውን ጊዜ መደበኛ ያልሆነ ሸንጎ ይመራሉ። የመስክ ሥራዬን በማከናውንበት ጊዜ አቶ ረዳና ሌሎች የአንድ አዛውንት ሸንጎ አባላት ሆነው ሲሠሩ ታዝቤያለሁ። በተለይ ሲያስችሉ ያየሁት አንድ ወጣት ሰው ከአንድ ሽምግል ካለ ግለሰብ ላይ ፈረስ ገዝቶ በክፍያና በርክክብ ላይ የተነሣውን ክርክር ነበር።

በቀጠሮው ቀን ፂማምና ሽበቶ የሆኑ አዛውንቶች ጋቢያቸውን ደርበው ሚዳዎችን አቋርጠው በመምጣት ገላጣ በሆነ ሥፍራ ላይ በሁለት ዛፎች ሥር ተኰለኰሉ። በቀረበላቸው አንድ ማንቆርቆሪያ ጠላ ጊዜያዊ መስተንግዶ እየተደረገላቸው እንዳለ ማንኛውም የሚወስነው ቅጣት በዋስ አማካይነት ተፈጻሚ እንደሚሆን በመገንዘብ የስብሰባው መሪ በቅድሚያ ሁለቱ ተከራካሪዎች ዘመድ አዝማዳቸው ባሉበት ዋስ እንዲጠሩ አደረጉ። ከዚያም አቶ ረዳና ሽማግሌዎቹ ሁለት ወገኖች የሚሉትን ለመስማት በተናጠል አነጋገሯቸው። ይህም የተደረገው በአንድ ላይ ቢያነጋግሯቸው በባለጉዳዮችና በምስክሮች መካከል ጭቅጨቅ እንዳይነሣና የፍርዱ ሂደት እንዳይደናቀፍ በማሰብ ነበር።

ሽማግሌዎቹ ጉዳዩን እንዳጠኑት ወጣቱ ከሽማግሌው አንድ ፈረስ በብር 24 ገዝቶ ቀብድ 16 ብር ሰጥቶ ቀሪውን 8 ብር ገንዘብ እንዳገኘ ከፍሎ ፈረሱን ለመረከብ ተስማምተው እንደነበርና ወጣቱ ቀሪውን ከፍሎ ፈረሱን ለመውሰድ ቢጠየቅ የመጀመሪያውን የቀብድ ክፍያ ሽማግሌው በመካዱ ነበር ክርክሩ የተነሣው። ሽማግሌዎቹ ለብዙ ሳምንታትና ሰዓታት እየተቀመጡ ጉዳዩን መርምረው ካጣሩ በኋላ አንድ ውሳኔ ላይ ደረሱ። ውሳኔውም «ሽማግሌው ገንዘቡን ይመልስ ወይም ፈረሱን ያስረክብ» የሚል ነበር። ብዙ ጊዜ እንደሚያጋጥመው ሽማግሌው ውሳኔውን ስለተቃወመ መብቱም የተጠበቀ ስለሆነ ሽማግሌዎች ጉዳዩን በጥሞና መመርመር ቀጠሉ።

ሽማግሌው መንቻካ ብጤ በመሆኑ ትዕዛዙንም ሳይፈጽም እንዲያውም ወደስብሰባው መምጣቱን አቋረጠ። ለብዙ ወራት ወደስብሰባው እንዲመጣ ቢለመንም አሻፈረኝ በማለቱ የአዛውንቶች ሸንጎ ባህላዊ ውግዘታቸውን ለማድረግ በማሰባቸው በላኩት የመጨረሻ ማስጠንቀቂያ «በሸንጎው እንድትገኝ፣ ካልተገኘህ

እንረግምሃለን፣» በማለት ትዕዛዝ አስተላለፉ። እርግማኑ የሚፈፀመው የተባረከው «መስኪ» ተብሎ የሚታወቀውን ጠላ በሚረገመው ሰው ስም መድፋት ነበር። የማይቀረው ውሳኔ ከሚስጥብኝ ብሎ በመፍራት በመጨረሻ ሽማግሌው ሸንጎው ፊት ቀርቦ ውሉን ለመፈጸም ተስማማ። ሆኖም ለውሉ ማስፈጸሚያ ከውል ውጭ በተጨማሪ 2 ብር እንዲሰጠው ተደረገ።

አንድ ውሳኔ ተቀባይነት ሲያገኝ ሁለቱን ተከራካሪዎች ድንጋይ አሸክሞ ማስታረቅ የተለመደ ስለነበር፡ በመጀመሪያ ሽማግሌው፡ ቀጥሎ ደግሞ ወጣቱ ድንጋይ ተሸክመው ተራ በተራ «ይቅር በለኝ» ከተባባሉ በኋላ ተሳስመው የመጨረሻው እርቅ ሆኖ በአዛውንቶች ሸንጎ ተመርቀው ተሰናበቱ። ሁሉም የሸንጎ አባላት በ«ካሣ» ሥነሥርዓት ያለፉ በመሆኑ ምርቃታቸው ከፍተኛ ግምት የሚሰጠው መሆኑን መረዳት ተገቢ ነው።

በአቶ ረዳና በሌሎች የሸንጎ አባላት የታዩት ሌሎች ክርክሮች ስለመሬት ይዞታ መብት፣ ሌሊት ሌሊት ድንበሮች ተገፍተው ስለሚገኙ የሚከሰቱትን ችግሮችና የመሳሰሉትን ያካትታል። ልዩ ልዩ ጉዳዮች ደግሞ አንድ ግለሰብ ውሻው በመግደሉ፣ ከአንድ አባወራ ራቅ ባለ የእርሻ ይዞታው ላይ ስልሣ ዛፎች ባልታወቀ ሰው ስለተወሰደበትና አንዳንድ ሰዎች ደግሞ ስለተሰደቡ ያቀረቡትን የካሣ ጥያቄ ይመለከት ነበር። አንድ ጉዳይ በአዛውንት ሸንጎ ሳያልቅ ለብዙ ጊዜ ከተጓዘና ሊያልቅ ካልቻለ ከፍ ወደአለ የቅማንት የፖለቲካና ሃይማኖት ድርጅት ይተላለፋል። ምን ጊዜም ቢሆን ቅማንቶች አንድ ጉዳይ በሸንጎዎቻቸው እንዲያልቅ ነው ፍላጐታቸው። ይህንኑ ለማጠናከር አቶ ረዳ «አንድ አይነድ፣ አንድ አይፈርድ» የሚለውን ጥቅስ በየጊዜው ያነሳሉ።

ክርስቲያን ቅማንቶችና ሸንጐዎቻቸው። በክርስቲያን ቅማንቶች ዘንድ ሁለቱም ዓይነት ባሕላዊ ሸንጐዎች አሉ። መደበኛው ሸንጐ በየወሩ አንድ ወይም ሁለት እሁዶች የሰንበቴ ስብሰባ ተብሎ በሚታወቀው የማኅበሩ አባላት በሚገኙበት ቀን ይደረጋል። ሽማግሌዎች በየዓመቱ በሚመረጡና እኩል ሥልጣን ባላቸው ሁለት መሪዎች ሰብሳቢነት ሥራቸውን ያከናውናሉ። በክርስቲያን ቅማንቶች ዘንድ ሽማግሌዎች በ«ካሣ» ሥነሥርዓት

ማለፍ ተፈላጊነት የሌለውና እንዲሁም እንደ አረማዊ-አሬታዊ ቅማንቶች የግድማኖት ተፅዕኖ በሽንጐዎች ላይ አይኖርም።

ነገር ግን በአንዳንድ የክርስቲያን ቅማንቶች ዘንድ በአረማዊ-አሬታዊ ሥርዓት የነበረው ኃላፊነት ወደ አማራው መዋቅር ሙሉ በሙሉ አልተሸጋገረም። ስለሆነም ያዛውንቶች ሽንጐዎች ውሳኔአ ቸውን ተግባራዊ በማድረግ ረገድ የባህላዊ አሠራሩን ትንሽ ለማሻሻል ጥረት እያደረጉ ቢሆንም አሁንም ከጥንቱ የቅማንት አሠራር ሥነሥርዓት ለመላቀቅ አልቻሉም። ለምሳሌ የሽንጐውን ውሳኔ ለማስፈፀም ከአስር ዓመት በፊት ክርስቲያን የሆኑት እንኳን ወደ ድግናው አሁንም መሄድ አለባቸው። እዚያ ሄደው ለእግዚአብሔር (ምዝግና) ፀሎት በማድረግ ውሳኔአቸውን አልተበልም ወይም ካሣ አልከፍልም ባለው ሰው ላይ ተገቢው ቅጣት እንዲወሰንበት ያደርጋሉ። ጥፋተኛ ነው የተባለው ሰው በምዝግና ተቀጥቶ መጥፎ ዕድል ቢያጋጥመው ወይም ጥፋቱን አምኖ ካሣውን ለተበዳዩ ቢከፍል፣ ተበዳዩ ወደ ድግናው ሄዶ የእንስሳ መስዋዕት በማቅረብ፣ በኅብረተሰቡ ላሉ አዛውንቶች ግብዣ ያደርጋል። በሁሉም ክርስቲያን ቅማንቶች ዘንድ በአዛውንቶች ሽንጐ የሚሰጠው የመጨረሻ ውሳኔ አጥፊውን በማውገዝ ጠላ መሬት ላይ በመድፋት ሲሆን ሰንበቴው ደግሞ ወንጀለኛ የተባለውን ሰው በመርገም ነው። ይህ «መስኪ» የተባለውን የተደገመበትን ጠላ በመድፋት የሚደረገው የእርግማን ባህል በአረማዊ-አሬታዊ ቅማንቶች ሲደረግ ከነበረው ሥነሥርዓት የተወሰደ ሆኖ እናገኘዋለን።

የቅማንት የአዛውንቶች ሽንጐዎች በኅብረተሰቡ ውስጥ በፍትሕ አሰጣጥ ረገድ የሚጫወቱት ሚና የክርስቲያን ቅማንቶች የሰንበቴ ማኅበራትም ሆኑ የክርስቲያን የአዛውንቶች ሽንጐዎች ካላቸው የፍትሕ አሰጣጥ ኃላፊነት በጣም የላቀ ነው። በነገራችን ላይ የሰንበቴ ማኀበራት በክርስቲያን አማራዎችም ያለ ሥርዓት ነው። ክርስቲያን ቅማንቶች አሁንም ቢሆን ወደ አማራው ባለሥልጣን ሳይሄዱ ጉዳያቸውን እርስ በእርሳቸው ለመጨረስ ነው ፍላጐታቸው። አሠራሩ ሁልጊዜ አንድነታቸውን ከማስጠበቁም በላይ ከሞላ ጐደል በአማራውና በቅማንቱ መካከል ያለው ግንኙነት ድንበር ተዘግቶ እንዲቆይ አድርጓል።



መደበኛ የአዛውንቶች ሸንጎ ሁለት ዓመት የፈጀውን የመሬት ክርክር ሲመለከቱ። የያዙት ረጃጅም በትር ውሻ ለመከላከል ይጠቀሙበታል።

ቢሆንም በሚቀጥሉት አስርና ሃያ አመታት ክርስቲያን ቅማንቶች ሙሉ በሙሉ የአማራን ባህል ተቀብለው በባህላዊ ውህደት አማራ (አምሃራ-ይዝድ) እንደሚሆኑ በእርግጠኝነት መናገር ይቻላል።

ሸንጎዎችና የውጭው ዓለም። የአዛውንቶች ሸንጎ ከቅማንት ኅብረተሰብ ውጭ ከሌላው ዓለም ጋር ግንኙነት በማድረግ የሚጫወቱት ሚና አለ። ከማኅበረሰባቸው ውጭ ከሚነጋገሩባቸውና ውሳኔ ከሚሰጡባቸው ጉዳዮች በጥቂቱ ለመጥቀስ ያህል፣ ከአማራው ኅብረተሰብ ጋር ግንኙነት በማድረግ በትብብር የሰው ጉልበት አዋጥቶ መንገድ ለመጠገንና እንዲሁም በአካባቢው ሚሲዮናውያን እንዲገቡም ሆነ እንዳይገቡ ተነጋግሮ ውሳኔ መስጠትን የመሳሰሉትን ያካትታል። ሌላው ደግሞ በአካባቢው ተጨማሪ አዲስ የመሰብሰቢያ አዳራሾችን ወይም አዲስ መንገዶችን በጋራ ለመሥራት የሚደረጉ የጋራ ግንኙነቶች ይኖራሉ።

## መካከለኛው የፖለቲካ ሥልጣን

በድሮው ዘመን ዝቅተኛ ቀሳውስት (አባጋሪየስ) እና ክብር የሆኑ ከፍተኛ ቀሳውስት (ከመዘና) አሁን ካላቸው የፖለቲካ ሥልጣን የበለጠ በፖለቲካው ስፌ ሚና ነበራቸው። በአሁኑ ወቅት ለስሙ ያህል አንዳንድ ክርክሮችን አዳምጦ መፍትሔ ከመፈለግና በኅብረተሰቡ ዘንድ ሰላም ሰፍኖ መልካም ግንኙነት እንዲኖር ምክር ከመስጠት በስተቀር ብዙም ኃላፊነት የላቸውም። ሆኖም ፍትህን በተመለከተ ወምበሩን ይረዳሉ።

ዛሬ አብዛኛው የፍትሕ ሥራ የሚከናወነው አፈሊቅ ተብሎ በሚታወቀው የወምበሩ ቃል አቀባይ ነው። አፈሊቁ ከክብር ዘር በወምበሩ የሚመረጥ ሲሆን በትርፍ ጊዜው ለሚሠራው ሥራ ተገቢውን ክፍያ ወምበሩ ይሰጠዋል። በኅብረተሰቡ ዘንድ ተቀባይነትና አክብሮት ያለው ብቻ ነው ለዚህ ሥራ ብቁ የሚሆነው።

ባለፉት ዘመናት አፈሊቁ ከቦታ ቦታ እየተዘዋወረ ለክርክሮች ውሳኔ ይሰጥ ነበር፣ እንዲሁም ኅብረተሰቡና ቀሳውስቱ የቅማንትን ሕግ እያከበሩ መሆኑን ይቆጣጠር ነበር። አፈሊቁ ቅጣት የመወሰንና ቅጣት የመሰብሰብ ሥልጣን ቢኖረውም በቀሳውስቱ ላይ ይህንኑ ሥልጣን የተጠቀመበት ጊዜ

በኅብረተሰቦች ዘንድ ብዙም አይታወስም። አያንዳንዱ ወምበር ብዙ አፈሊቆች የነበሩት ቢሆንም የአረማዊ-አሪታዊ ቅማንት ቄተር በፍጥነት እየቀነሰ በመምጣቱ ክፍት በሆኑት የአፈሊቅ ቦታዎች ሌላ ሰው መተካት አስፈላጊ ሆኖ አልተገኘም። አፈሊቁ ሊወስናቸው ያልቻላቸው ችግሮችና ጉዳዮች ለወምበሩ እየቀረቡ ተገቢውን ውሳኔ ያገኛሉ።

## ወምበር፡ የመጨረሻው ዳኛ

ወምበሩ የቅማንት ቀሳውስት የበላይ ብቻ ሳይሆን የፍትህና የአመራር ሥልጣን ያለው ሰው ነው። በመካከለኛ ደረጃ በሚገኘው የፖለቲካ ሥልጣን አካላት ሊፈቱ ያልቻሉ ክርክሮች ወይም ጥሎች ወደ እሱ ይመራሉ። ቅማንቶች በአስገዳጅ ሁኔታዎች የአማራን ባህል እንዲቀበሉ ከመደረጉ በፊት በከርከር አንድ የበላይ ወምበር፣ በጭልጋ ደግሞ አንድ ሌላ የበላይ ወምበር፣ በአጠቃላይ ሁለት ወምበሮች ነበሩ። ከወምበሮች ቀጥሎ አስር የሚያህሉ ንዑስ ወምበሮች የነበሩ ሲሆን፣ ከጓንግ ወንዝ በስተምስራቅ ያሉት በከርከር ወምበር ሥር፣ ከጓንግ ወንዝ በስተምዕራብ የነበሩ ደግሞ በጭልጋ ወምበር ሥር ይታዘዙ ነበር። በጣም አስቸጋሪ ጉዳይ ካላጋጠማቸው በስተቀር ንዑስ ወምበሮቹ ማንኛውም ለሚቀርብላቸው ክርክሮች ሁሉ ውሳኔ ይሰጡ ነበር። እ.ኤ.አ. በ1900 ዓ.ም. መጀመሪያ አካባቢ ሁለቱ የበላይ ወምበሮች ብቻ ቀሩ። ከሁለቱ ወምበሮች የከርከሩ ወምበር ላቅ ብሎ ስለሚታይ «ታላቁ ወምበር» እየተባለ ይጠራል። እ.ኤ.አ. በ1955 ዓ.ም. የከርከሩ ወምበር ከሞቱ ወዲህ በምትክ ሌላ ወምበር ሳይሾም በመቅረቱ በአሁኑ ጊዜ የጭልጋው ወምበር ብቻ ነው በመላው የቅማንት አገር የሚገኘው።

ከወንበሩ ፊት መቅረብ። ወምበሩ አብዛኛውን ጊዜ ከከመዘናውና (ከፍተኛው ቄስ) በኅብረተሰቡ ከሚገኙ ቀሳውስት ጋር ሆኖ ነው አቤቱታዎችን የሚቀበለው። ሦስቱም አካላት ከሳሽንና ተከሳሽን በማነጋገርና አስፈላጊ የሆኑትን ጥያቄዎች በመጠየቅ ከመጨረሻ የውሳኔ ሃሳብ ላይ ይደርሳሉ። ነገር ግን የመጨረሻውን ውሳኔ የሚሰጠው ወምበሩ ነው። ጉዳዩ የሚመለከታቸው ደጋፊዎችና ምስክሮች ዋሽተው ከተገኙ ምዝግና እንደሚቀጣቸው አስቀድሞ ማስጠንቀቂያ ይሰጣቸዋል። ከሳሽና ተከሳሽ ለክሱ ተመጣጣኝ ነው የተባለ ለዳኝነት ከብት ወይም ሰብል ወይም እህል ብዛቱን ወይም ስፋቱን ገልጸው ዋስትና

(ቦንድ) ማቅረብ አለባቸው። በመጨረሻ ከሁለቱ አንዱ የተረታው ለዋስትና ያስያዘው ንብረት በመቀጫ ስም ገቢ ይሆንና ወምበሩ ከዚሁ ድርሻውን ያገኛል።

ክርክሮች በመረጃዎች አለመሟላት ምክንያት ዳር ሊደርሱ ካልቻሉ ወይም በሁለቱ ወገኖች በኩል የተነገረው ታሪክ እኩል ሚዛን ከደፋ ወምበሩ ከሳሽና ተከሳሽን በአቅራቢያው ወደሚገኘው ቅዱስ ድግና (ደን) ይወስዳቸዋል። ከዚያም በወምበሩ ትእዛዝ መሠረት ቀሳውስቱ ለተከሳሹ መጥረቢያና ማጭድ ይሰጡታል። ተከሳሹ በያዘው መሣሪያ በድግናው ከሚገኙ አንዱን ዛፍ ቆርጦ መጣል ስላለበት በሚቆርጥበት ጊዜ ጮክ ብሎ «ወንጀለኛ ሆኜ ከተገኘሁኝ ይህን ዛፍ እንደቆረጥኩት ምዝግና እኔንም ይቆራርጠኝ» ማለት አለበት። ተከሳሽ በእርግጥ ወንጀለኛ ከሆነ የሚመጣበትን መቅሰፍት በመፍራት ገና መሣሪያውን ሳይነካ ጥፋቱን በመናዘዝ ንስሀ ይገባል። ንፁህ መሆኑን ካመነ ግን ዛፉን ለመቁረጥ ወደኋላ ስለማይል እርግማኑ ውሸታም ወደሆነው ከሳሽ እንዲተላለፍ ይደረጋል። ከሳሹ የሐሰት ማስረጃ ማቅረቡን ወይም ተከሳሹ የመቁረጫ መሣሪያውን ከመቀበሉ በፊት ስለጥፋቱ በማመን ንስሀ ከገባ ማንኛውንም ቅጣት በቀጥታ ሁለቱም ወገኖች ግማሽ ግማሹን ይከፍላሉ።

በመጨረሻ ውሳኔ ላይ ሲደረስ ወምበሩ የገንዘብ መቀጫ ይጥላል። ከዚህም በስተቀር ንብረቶችን ወደ ትክክለኛው ባለ ሀብት ይመልሳል፤ መሬትን የሚመለከት ክርክር ከሆነ ሕጋዊ ባለመሬቱ ማን እንደሆነ ያረጋግጣል፤ ተራ ለሆኑ የሃይማኖት ሕጉች መጣስ አጥፊው ለሰባት ሌሊት ባዶ መሬት ላይ እንዲተኛ ወይም ለሰባት ቀን ኮሶ እንዲጠጣ ወይም በየቀኑ ውሃ በማመላለስ ሰውነቱን እንዲታጠብ ሊወሰን ይችላል። እንዲሁም ቅዱስ ቦታዎችን ማርከስ፣ ለሃይማኖት አባቶች ተገቢውን አክብሮት አለመስጠትና በዓላትን በተገቢው ሥነሥርዓት አለማክበር ለወምበሩ እስከ ሁለት አሞሌ ጨው ሊያስከፍሉ የሚችሉ ጥፋቶች ናቸው።

ወምበሩ የቅማንት የጥንት ባህሎችና ልምዶች ተጠብቀው እንዲቆዩ በጣም የሚያስፈሩ፣ ማለትም የቀብር ሥነሥርዓት ከመከልከል ጀምሮ እስከ ገነት መግቢያ በሮችን መዝጋት ድረስ የሚደርስ ቅጣት ይወስናል። እርግማንና ከኅብረተሰብ ማግለል

በወምበሩ የሚስነዘሩ ቅጣቶች ሲሆኑ አብዛኛውን ጊዜ ተግባራዊ የሚሆኑት የእሱን ሥልጣን በሚቀናቀኑት ላይ ነው። ለምሳሌ አንድ ግለሰብ የወምበሩን ውሳኔ ሳይቀበል ቢቀር፣ መሠረታዊ ከሆነው ከቅማንት ሃይማኖታዊ ሥርዓት ውጭ ጋብቻ ቢፈጽም ከኅብረተሰቡ ይገለላል። ከኅብረተሰቡ መገለል ማለት የማይሻርና የማይለወጥ እንዲያውም ስውዬው ከሞተም በኋላም ተግባራዊ የሚሆን ውሳኔ ነው። የተወገዘ ወይም የተገለለ ሰው ቀብሩ በሥነሥርዓት አይፈጸምም፣ ወደገነት ያስገባል ተብሎ የሚደረገው ሥርዓተ-ቅዳሴ ስለማይደረግለት ወደገነት መግቢያ በር ሁሉ እንደተዘጋበት ይቀራል።

<u>ነፍስ ግድያና</u> ወምበሩ። ለወምበሩ የሚቀርብ በጣም የከፋ ወንጀል ቢኖር ነፍስ ግድያ ነው። ለቅማንቶች ድንገተኛም ይሁን ወይም በመከላከል ወቅት የሚደርስ ግድያ በአጠቃላይ የሰውን ነፍስ ማጥፋት ማለት ስለሆነ በነፍስ-ገዳይነት ነው የሚያስጠይቀው። የቅማንት ሕግ «ዓይን ያጠፋ ዓይኑ ይጥፋ» ስለሚል የአንድ ሰው ሕይወት ያጠፋ ግለሰብ የሚሰጠው ፍርድ ሕይወቱ በሟች ዘመድ እንድታልፍ ማድረግ ነው። ምርጫ ባይኖርም አንድ እርዳታ ግን ሊደረግለት ይችላል። ይኸውም ዘመዶቹ የደም ካሣ ከፍለው እንዲታረቁ ማድረግ ነው። ከሃምሣ ዓመት በፊት የደም ካሣ 80 ማርያ ቴሬዛ ብር ነበር። አሁን ግን ዝቅተኛው አራት መቶ ብር ሆኖ አንዳንድ ጊዜ ከ700 እስከ 1000 ብር ይደርሳል።

የገዳይ ቤተሰቦች ከሟች ቤተሰብ ጋር በሽንጉዎችና በሌሎች አስታራቂዎች አማካይነት ስምምነት ላይ መድረስ ካልቻሉ ወምበሩ በጉዳዩ ጣልቃ ይገባል። ከሁለቱ ወገኖች ስምምነት ከተደረሰ መከፈል የሚገባው ካሣ በወምበሩ ወይም በአዛውንቶች ሽንጉ አማካይነት የቃል ስምምነት ይገባሉ። ይህም ስምምነት በሁለቱ በኩል ለመንግሥት ሹማምንት ይሰጥና እነሱም በተጨማሪ ለወንጀሉ መከፈል የሚገባውን የገንዘብ ቅጣት ከጥፋተኛው ተቀብለው ለግድያ የተጠቀመበትን ማሣሪያ በመግፈፍ በውርስ ለመንግሥት ገቢ ያደርጋሉ። በዚህም መሠረት መንግሥት ስለነፍስ ገዳዩ ወንጀል በቅማንቶች የተሰጠውን ውሳኔ አፀደቀ ማለት ነው። በስምምነቱ መሠረት አስፈላጊው ሁሉ ከተሟላና የመንግሥት ቅጣት ገቢ ከሆነ በኋላ ገዳዩ ላይ በተጨማሪ ሌላ ቅጣት እንዳይደርስበትም ፋይሉ ይዘጋል።

እስከቅርብ ጊዜ ቅማንቶችን የሚመለከት ክስ የአማራው መንግሥት ለጭልጋ ወይም ለከርከር ወምበር ያስተላልፍ ነበር። ወምበሩም ምን እርምጃ እንደወሰደ ለመንግሥት ያስታውቅ እንደነበር ነው። ዛሬ የደም ካሣ ጉዳይ አከራካሪ ሆኖ ከተገኘ ለመንግሥት ዳኞችና አስተዳዳሪዎች ይተላለፋል። በመንግሥት በኩል ክሱ እልባት ካላገኘ አልፎ አልፎ እንደሚያጋጥመው የገዳይ ወገኖች ገዳዩን በመግደል የሟችን ደም ያበቀላሉ። ከዚያ በኋላ የማያቋርጥ ደምን በደም የመመላለሱ ሁኔታ ሊቀጥል የሚችል ቢሆንም ብዙ ጊዜ አያጋጥምም። ይህ አጋጣሚ እንዳይፈጠር በአሁኑ ጊዜ የኢትዮጵያ መንግሥት ነፍስ ገዳዮች እየተያዙ ተገቢውን ፍርድ እንዲያገኙ በማድረግ ላይ ነው።

የወምበሩ ሀብት። ከቅስናው ዓለም ከሚሰጠው ሥልጣን በተጨማሪ ወምበሩ ሀብት በማካበት ኃያልነቱን ያጠናክራል። ለሥነሥርዓቶች የሚደረጉ መዋጮዎች፣ የተወረሱ የዋስትና ንብረቶች፣ የሃይማኖት ሕግጋትን በመጣስ ከሚጣል የሚገኝ የቅጣት ገቢ የመሳሰሉት ሊጠቀሱ የሚችሉ የገቢ ምንጮቹ ናቸው። ከዚህም በስተቀር በግል ከሚያካሂዳቸው ሥነሥርዓቶች ሁለት አሞሌ ጨው ወይም ሁለት ማርቴሬዛ ብር ያገኛል። በወምበሩ የሚባረኩና በቀሳውስት የሚካሄዱ ቅስናንና የአካባቢ ጭቃ ሹምነትን ማዕደትና የጉት በር እንዲከፈት የሚያደርጉ ሥርዓተ-ቅዳሴዎች በዚህ ውስጥ የሚካተቱ ናቸው። እስከ አለፈው 19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን መጨረሻ ድረስ የከርከር ወምበር በምሥራቅ በኩል ከሚገኙት የቅማንት ኅብረተሰብ፣ የጭልጋው ወምበር ደግሞ ከምዕራብ የቅማንት ኅብረተሰብ ግብር ይሰበስቡ ነበር። ይህ ዓይነቱ ግብር በከርከር አካባቢ በግዴታ የአማራን ባህል እንዲቀበሉ ማስገደድ ከተጀመረበት በ1880ዎቹ ዓ.ም. በጭልጋ ደግሞ በ1920ዎቹ ዓ.ም. እንዲቋረጥ ተደርጓል።

ዋናው የወምበሩ የሀብት ምንጭ ግን በኩዳድ በኅብረተሰቡ ከሚታረስለት መሬት የሚያገኘው የሰብል ምርት ነው። ወምበሩ ያለው ሥልጣንና ክብር ሁኔታዎቹን ስላላመቻቹለት ከማንኛውም ገበሬ የበለጠ አንድ ቤተሰብ ሊያርሰው የማይችል የእርሻ መሬት ስላስገኘለትና ይኸውም መሬት በሕዝቡ ጉልበት በኩዳድ ስለሚታረስለት ብዙ ምርት ያገኛል።

# ምዕራፍ ሰባት

## ማኅበራዊ አደረጃጀት

ቅማንቶች እንደሌሎች በቅድመ-ኢንዱስትሪ ዘመን አካባቢ እንደነበሩ ሕዝቦች ሁሉ በሠለጠኑት እንደአሜሪካ ባሉት አገሮች ጉልቶ የማይታይ እንደሸረሪት ድር የተጠላለፈ የዝምድና ትስስር አላቸው:: ገጠሬና ኋላቀር በሆኑ ኅብረተሰቦች የእያንዳንዱ ግለሰብና ኅብረተሰብ ሕልውናና ደኅንነት ተጠብቆ የሚገኘው ውስብስብ የሆነውን የዝምድና ግንኙነት በማጠናከርና ዘመድ አዝማድን በማበራከት ነው:: አልፎ አልፎም አንዳንድ ግለሰቦች የሥጋ ዘመዶቻቸው ብዛት ውስንና ጠባብ ከሆነባቸው ሠፊ ወገን ለማግኘት በመሻት የሥጋ ዝምድና ባይኖራቸውም የቃል ኪዳን ማኅበራዊ ዝምድናን ለመመሥረት ጡት በማጥባትና አበልጅ በማድረግ ዝምድናን አስፋፍቶ ባለብዙ ወገን ለመሆን ጥረት ያደርጋሉ:: አንዳንዶቹም የወገኖቻቸውን ደኅንነት ለማስጠበቅና አንድነታቸውን ለማስተሳሰር በማኅበር መደራጀታቸው የታወቀ ነው::

በዚህ ምዕራፍ የምንመለከተው እንግዳ የሆነው የኅብረተሰብ ማኅበራዊ አደረጃጀት በመጀመሪያ ሲያጋጥም ውስብስብ፣ ከባድና የማይገባ መስሎ ሊታይ ይችላል:: አንዳንድ ልዩ የሆኑ አዲስ ቋንቋዎች ሲያጋጥሙን ግር እንደሚለን ሁሉ ለጉዳዩ እንግዳ በመሆናችን ስላልተለማመድነው የሚደርስ ችግር ነው:: በሚገባ ከተረዳነው ጥልፍልፍ የሆነው የቅማንት የዝምድና ሐረግ ምጥን የሆነ ነገር ግን ግትር ያልሆነ የእርስ በእርስ ግንኙነትን የሚያበረታታ ማኅበራዊና ባህላዊ ሥርዓት መሆኑን እንገነዘባለን:: የቅማንት የዝምድና ትስስር ሁኔታ ከአካባቢው ተፈጥሮአዊ ሁኔታዎች ጋር ከመለማመድ የተነሣ የተገኘ ውርስ ነው::

## ባለአንድ ሐረግ የዝምድና መዋቅር

የአረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖት በቅማንቶች ዘንድ መኖሩ በኢትዮጵያ ሥነ-ጽሑፎች ብዙ የተባለለት ስለሆነ አዲስ ነገር ስላልሆነ አያስገርምም:: ነገር ግን ጥንድ የሆኑ የትውልድ የዘር አብራክ ክፋዮች አንድ ወጥ የሆነ ሐረግ ተከትለው እስከ መጨረሻው በመዝለቅ በሁለት ቡድኖች (ፓርቲ) ተደራጅተው

መገኘታቸው ነው የሚያስደንቀው:: የዚህ ዓይነት የኅብረተሰብ አደረጃጀት በተለይ በሌሎች አገዎች፣ በአማራውና በትግሬው ሕዝብ ዘንድ የመኖሩ ምልክት ፈጽሞ አይታይም:: ይህን ዓይነት አንድ ወጥ የሆነውን የዘር ሐረግ አደረጃጀት ፍንጩን ያገኘው ማርቲን ፍላድ ሲገልጸው፣ «ቅማንቶች በሁለት ቡድኖች (ፓርቲ) የተከፈሉ ናቸው:: የበላይ የሆነው «ክብር»፣ እና በደረጃ ዝቅ ብሎ የሚታየው ደግሞ «የታንቲ» ይባላል» ይላል:: (1866:20-21) :: በዚህ ምዕራፍ የምንመለከታቸውን የዝምድና ስያሜዎች በምዕራፍ አንድ «የኅብረተሰቡ ትስስር ምክንያት» በሚለው ንዑስ ርእስ ላይ ተብራርቷል::

<u>የአባት የዘር ሐረግና ጋብቻ</u>:: ሁሉም ቅማንቶቸ «ክብር» ወይም «የታንቲ» ናቸው:: እነዚህ የዘር ክፋዮች በክልል የተወሰኑ ሳይሆኑ በአረማዊ-አሪት ሃይማኖታቸው በአንድ ላይ የተሳሰሩ ናቸው:: በአሁኑ ጊዜ ለአንድ ትውልድ ያህል ክርስቲያን ሆነው የቆዩት ቅማንቶች ብዙም ከቁምነገር አይቆጥሩትም:: የ«ክብር»ና የ«የታንቲ» የዘር ክፍያዎች በአባት የዘር ሐረጋቸው የሚለዩ ሲሆን የቅስና ደረጃን ለማግኘት የአባት የዘር ግንድ ወሳኝ ነው::

በአንድ የዘር ግንድ ያሉ ሰዎች ጋብቻቸው ከውጭ እንጂ እርስ በእርሳቸው አይጋቡም:: የመጨረሻው የከርከር ወምበር ልጅ እንደነገሩኝ አንድ «ክብር» ሌላ «ክብር» ሴት ወይም አንድ «የታንቲ» ሌላዋን «የታንቲ» ቢያገባ ልክ እህቱን እንዳገባ ነው የሚቆጠረው:: ሆኖም የጋብቻው ሕግ ተራ የዝምድና ክፋይ ሐረጉችን አይመለከትም:: (ስለዝርዝሩ መግለጫ ቁጥር ሁለትን ይመልከቱ)::

ጥብቅ የሆነው የጋብቻ ሕግ በኅብረተሰቡ ዘንድ የተከለከ ለውን የዘመዳሞች የእርስ በእርስ ጋብቻን ሲቆጣጠረው ቆይቷል:: ከዚህም በስተቀር ቀደም ብሎ እንደተጠቀሰው ቀሳውስቱ ከቀብር ሥነሥርዓት ማገድ ጀምሮ እስከ ገነት በር መዝጋት ውግዘት የሚደርስ የሚያስፈራ ቅጣት ስለሚወስኑ የሕጉ ተግባራዊ መሆን አጠያያቂ አልነበረም:: በመሆኑም ማንም ይህን ሕግ ለመጣስ ስለማይፈልግ ቅማንት ያልሆነ ሌላ ሰው ውስጣቸው አይገባም፣ እስከቅርብ ጊዜ ድረስም ከእነሱ መካከል በጋብቻ ምክንያት ይህን በቅርብ የተሳሰረ ኅብረተሰብ ጥሎ የሄደ የለም:: ስለዚህ ይህ ጭምር አደረጃጀት በወምበሩና በቀሳውስቱ ጥበቃ እየታገዘ

ሕብረተሰቡ ከሌላው ሕዝብ ጋር እንዳይገናኝ አጥር ሆኖ ኖሯል:: ምንም እንኳን የቅማንት አፈ-ታሪኮች፣ የኢትዮጵያ ዜና መዋዕሎችና አገር ጎብኝ አውሮጳውያን ብዙ ሚስቶች ማግባት የተፈቀደ እንደነበረ ቢገልጹም፣ በቅማንት ኅብረተሰብ ጋብቻ አንድ ለአንድ ነው የሚፈቀደው:: እቁባት መያዝ አለ፡ ቢሆንም በሕጋቸው መሠረት ከአንድ ሚስት በላይ ማግባት የተከለከለ ነው::

ማቸውም ቅማንት ወንድም ሆነ ሴት በአጠቃላይ «ከብር» ወይም «የታንቲ» ተብሎ ይታወቃል:: የግለሰቡን ያታና ትክክለኛ ደረጃቸውን ለመረጋገጥ አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ ሁሉም ከብር ወንዶች ከብር ተብለው ይጠራሉ፣ እንዲሁም የየታንቲ ወንዶች የታንቲ ይባላሉ:: ይህ ሊሆን የሚችለው ግን የየታንቲ ወንድ ልጅ ልጅ ከሆኑ ነው:: (መገለጫ ሁለትን በድጋሚ ይመልከቱ)::

አንድ ወንድ ወይም ሴት የየታንቲ ዘር ሆኖ/ሆና የአንድ ወንድ የከብር የልጅ ልጅ (ወንድ ወይም ሴት ይሁን) «ሰንከራይሁራ» ተብለው ይጠራሉ:: («ሁራ» ማለት ልጅ ማለት ነው):: የከብር ዘር የሆነች ሴት አባቷ ከብር ከሆነ «ሰንከራ»ትባላለች:: የየታንቲ የዘር ክፍይ ያላት ነገር ግን «ሰንከራይሁራ» ካልሆነች «እናዝቴ» ትባላለች፤ የታንቲ የሆነ ወንድ የልጅ ልጅ ናት:: የትውልድ ሐረግ የአባት የዘር ግንድን ተከትሎ ስለሚታይ ልጆች የአባታቸውን የዘር ሐረግ ተከትለው ነው የሚቆጠሩት:: ነገር ግን የጋብቻ አፈጻጸምን በተመለከተ ጥንድ የሆነው አደረጃጀት በንዑስ ዘርፎች በቀላሉ አይለይም:: የታንቲ የሆነ አባት ያላቸው እና «ሰንከራ» የሆነች እናት ያላቸው ልጆች ከጋብቻ በስተቀር በማንኛውም ረገድ የ«የታንቲ» ደረጃ ተሰጥቶአቸው «የታንቲ» ወይም «እናዝቲ» ተብለው የሚጠሩ ሳይሆን «የሴንከራ ልጅ» ተብለው ነው የሚታወቁት:: «ሴንከራሁራ» ደረጃው ከብር ለመሆን የተቃረበ ስለሆነ ከከብር ጋር አይጋባም:: ይህ የሚያመለክተው የከብር ከፍተኛ ደረጃን ለመጠበቅ ያህል የከብር የልጅ ልጆችን እንኳን ይህን መብት ይነፍጓቸዋል::

ከቅርብ ዘመድ ጋር የግብረ-ሥጋ ግንኙነት ማድረግና ጋብቻ መፈፀም በማንኛውም የቅማንት የዘር ክፋዮች የተወገዘ

ሲሆን በደም የተገናኙ ከሆነም ስባት ትውልድ ቆጥረው መጋባት እንዳለባቸው ነው። ባለፉት አርባ ዓመታት ትግንቶች ይህን የጋብቻ ባህል ወደ አራት ትውልድ ዝቅ ያደረጉት ቢሆንም የጥንቱ ሕግ የተሻለ መሆኑን የሚናገሩ አሉ።

በክብርና በየታንቲ ያለው ልዩነት። ቀደም ብሎ እንደተ ገለፀው ወምበሮች፣ ከፍተኛ ቀሳውስትና ከፍተኛ የሃይማኖትና የፖለቲካ መሪዎች እንዲሁም የወምበሩ አፈሊቅ (ቃል አቀባይ) እና ዋናው የእልፍኝ ኃላፊ ከክብር የዘር ሀረግ ካላቸው ነው የሚመረጡት። ዝቅተኛ ቄሶች «መስኪ» የተባለውን የተቀደሰ ጠላ (ጠበል) የሚጠብቁት ደግሞ ከየታንቲ ዘር ነው የሚመረጡት።

እስከቅርብ ጊዜ ድረስ አንድ የክብር ሽማግሌ መደበኛ ያልሆነ የአስታራቂነትና የአማካሪነት ሥራ ስለሚሠራ በፍትሕ በኩል ያለው የሥራ ድርሻ ቀላል አይደለም። አንድ የታንቲ ወይም ሲንክሬይሁራ በደል ከደረሰበት የክብሩን ጉልበት በመሳም ችግሩን ይገልጻል። የክብር ሽማግሌው በቀሳውስት በኩል ከፍተኛ ውግዘትም ሆነ እርግማን እንደሚደርስ በማግባባት ያስታርቃል። ለክብር ሽማግሌው የተሰጠው ሥልጣን በክብርና በየታንቲ ላለው የመደብ ልዩነት አንዱ ምልክት ነው። ሆኖም በአሁኑ ዘመን በማስታረቁ ሥራ የሚጫወቱት ሚና በክብር ወይም በየታንቲ ወይም በሲክራይሁራ ሽማግሌዎች መካከል ልዩነት አይታይም።

ዛሬ ባለባበስ፣ በቤትና በመሣሪያ እንዲሁም በመሬት ይዞታ በክብርና በየታንቲዎች ልዩነት ባለመኖሩ በሀብት በኩልም አንዱ ከሌላው አይበልጥም። አንዳንድ ሰዎች ክብሮች ከየታንቲዎች የበለጠ በርካታ መሬት የነበራቸውና ያላቸው ናቸው ቢሉም ይህንኑ በተጨባጭ የሚያረጋግጥ ማስረጃ አልተገኘም። ከሠላሣ ዓመት በፊት ግን በተለያዩ ሥነሥርዓቶች ክብሮች ከየታንቲዎች ተለይተው በተሻለ መቀመጫ ይቀመጡ እንደነበር ይነገራል። ክብሮች ምግብና መጠጥ እንዲሁም የእጅ ውሃ በመታጠብ ቀሳውስት ከተስተናገዱ በኋላ ከየታንቲዎች ቀድመው (ቀሳውስቱን ሳይጨምር) ይሰጣቸው ነበር። ከአንድ መቶ ዓመት በፊት ወጣት ክብር ለአንድ ሽማግሌ የታንቲ መጠጥ እንኳን አይቀዳለትም፣ ነገር ግን የየታንቲ ሽማግሌ ለወጣቱ ክብር መጠጥ መቅዳት

መግለጫ ቁ2 የቅማንት የጋብቻ መመሪያ

ከ: ከብር (የከብር ዘር ክፋይ በአጠቃላይ)
የ: የተንቲ (የየታንቲ ዘር ክፋይ በአጠቃላይ)
ከ: የከብር (የወንድ የከብር ዘር ክፋይ)
የ: የታንቲ ( ወንድ የየታንቲ ዘር ክፋይ «የየታንቲ ወንድ ልጅ ልጅ»)
ሰ: ሰንከራ (የሴት የከብር ሀረግ «የከብር ሴት ልጅ»)

ሀ: ሲንከራሁራ (የየታንቲ ዘር ክፋይ የሰንከራ ልጅ)
አ: አናዛቲ (የየታንቲ ሀረግ ክፋይ የየታንቲ ሴት ልጅ)



(ማኅለፍ) ባሕሉ ይፈቅድ ነበር። እንደ የታንቲ እንደ ክብርን በመንገድ ላይ ሲያገኝ እጅ ይነሳል፡ አሁን የማይደረግ ቢሆንም ጉልበት መሳምም ይጠበቅበት ነበር።

በአጠቃላይ በቅማንት ኅብረተሰብ የየታንቲ ዘር ከክብር በዝቅተኛ ደረጃ ይታይ ስለነበር ሁለት የኅብረተሰብ መደቦች እንደነበሩ የሚጠቁም ነው። ሌላው በግልጽ የሚታወቀው ሦስተኛው ዝቅተኛ ደረጃ መደብ ደግሞ በውርስ የተገኙትን ባሪያዎችን (አገልጋይ) የሚያጠቃልል ነው። እነዚህ እንደባሪያ የሚያገለግሉት ጥቁሮች የተገኙት ከቆላማው ምዕራብ ኢትዮጵያ ክፍል ነው። ድሮ በቅማንቱ ክልል በባሪያነት ሲያገለግሉ የነበሩት በአሁኑ ወቅት ነፃ ቢሆኑም መሬት ስለሌላቸው «በእኩል አራሽነት» ወይም በግርድናም ሆነ በሎሌነት ተቀጥረው ይሠራሉ። አንዳንድ ሰዎች ከባሪያቸው ልጅ ሲያስወልዱ ልጁን «ውላጅ» ማለት የተለመደ ነበር። በባሪያው አሳዳሪ ዘመን አንዳንዶቹ ሴት አገልጋያቸውን በመወሽም ሌሎች ደግሞ እንዳጋጠማቸው የግብረ-ሥጋ ግንኙነት በማድረግ ሴትዮዋ አርግዛ ልጅ ከወለደች ጌታዋ ልጁን የግል አገልጋይ ያደርገው ነበር።

የአባት ጉሣ፡ የክብር የቃል ዘር ቆጣሪዎች የአባትን የዘር ሐረግ በመከተል እስከ አሥራ አራት ትውልድ በመቁጠር ጥንታዊ ከሆኑት በግልጽ ከተከፋፈሉት ዘጠኙ የባሕል ጀግኖችና የጉሣ መሥራቾች ጋር ያገናኙታል። (መግለጫ ቁጥር አንድን ይመልከቱ)። የታንቲዎች በዚሁ መልክ ትውልዳቸውን የሚቆጥሩ ቢሆንም የተለየ የባሕል ጀግና ስለሌላቸው የጉሳ መለያ የላቸውም። ብዙዎቹ የየታንቲ ዘር ቆጣሪዎች መጨረሻ ላይ እንደምንም ብለው ከክብር የባሕል ጀግና ጋር ያገናኙታል። እንደ ቅማንቶች አባባል ክብር «ንፁሕ ቅማንት» ሲሆን የታንቲዎች ግን ካልታወቁ ሌሎች ሕዝቦች ጋር ተጋብተው የተዳቀሉ ናቸው ይሏቸዋል።

ዛሬ የክብርና የየታንቲ የኅብረት ማኅበራት ለምሳሌ የጋራ ንብረት ወይም የተለየ የግዛት ይዞታን የመሰለ ነገር ባይኖራቸውም የሠፈሩ መሬትን በተመለከተ በአካባቢዎች ተወስነዋል። ይኸውም ናዚ፣ የንጋሲ እና የዛና የተባሉት የክብር ክፋይ ጉሣዎች የቅማንት ምሥራቃዊ ክፍል በሆነው በከርከር አካባቢ ተሠራጭተው ይገኛሉ። (መግለጫ ቁጥር አንድን

ይመልከቱ):: ይህም ከብዙ መቶ ዓመታት በፊት ምናልባት ግዛታቸው በደንብ የተለየና ጠንካራ የሆነ ማኅበራዊ ድርጅት እንደነበራቸው ያስገነዘበናል:: ቁንጮው ላይ የነበረውን እያንዳንዱን የባህል ጀግና ለማስታወስ በራሱ ስም የተሰየመ አንድ ወይም ከዚያ በላይ ድግና (ቅዱስ ደን) አለ:: በቅማንት እየተረሱ ከመጡት ቁንጮው ላይ ከነበሩት አባቶች ጋር ያለው በጣም የሳሳ የግንኙነት ሰንሰለት ቢኖር በድግናዎች ለባህል ጀግኖች መታሰቢያ የሚደረገው መስዋዕት ብቻ ነው::

የአባትን የዘር ሐረግ ተከትሎ የሚደረገው የጐሣ ቆጠራ ለመሬት ይዞታ ባለቤትነት አይጠቀሙበትም፣ ነገር ግን ለአንድ የፖለቲካና የሃይማኖት መሪነት ምርጫ አስፈላጊ ነው:: በዚህ ሁኔታ የትውልድ ሐረጉን በመምዘዝ እንማን በፖለቲካና በሃይማኖት መሪነት ተመርጠው እንዳገለገሉ እንደሚስረጃ አድርጉ ማቅረብ የተለመደ ነው:: ማንኛቸውም ሦስቱ የከብር ዘር የሆኑት የከርከር ጐሣዎች ወይም በጭልጋ የሚገኙት የጐሣ ቅርንጫፎች ለከርከርና ጭልጋ ወምበር ለመሾም በቅደም ተከተል ለየአካባቢያቸው እጩዎችን ማቅረብ ይችላሉ:: በተመሳሳይ ሁኔታም ለቅስና እና ለአንዳንድ አነስተኛ የፖለቲካና የሃይማኖት መሪነት እጩዎችን ያቀርባሉ:: ዝቅ እያለ ሲወርድ ብዙ የአባት የዘር ሐረግ ክፍልፋዮች ስለሚኖሩ ቀሳውስት ከነዚህ ውስጥ ሊመረጡ ይችላሉ:: ሆኖም በአሁኑ ጊዜ የዘር ሐረጉች ፋይዳ ስለሌላቸው እንደ ጥንቱ የተለዩ ስያሜም አይሰጣቸውም::

አንድ ወጥ የሆነው የአባት የዘር ሐረግ ቆጠራ በአሁኑ ጊዜ የሚነሣበት ምክንያት ቢኖር የጋብቻ ሕግንና ሃይማኖትን በተመለከተ ብቻ ነው:: ከአንድ ወጥ የዘር ሐረግ ቆጠራ ጋር የተያያዙ ሌሎች ልማዶችም አሉ:: አንድ ልጅ የአባቱን አንደኛ ወይም ዋና ስም ለራሱ የመጨረሻ ስም አድርጉ መውሰድ፣ እንዲሁም ቆሌና ዛሮችም ወደ ቤተሰብ የሚሸጋገሩ ስለሆነ የአባት የሆነው ለወንዶች፣ የእናት የሆነው ደግሞ መስመሩን ተከትሎ ወደ ሴት ልጅ ይተላለፋል::

ከጋብቻ በኋላ ባልና ሚስት የራሳቸውን ቤት ሠርተው ጉጆ እስከሚወጡ ድረስ ሁለት መኖሪያ ይኖራቸዋል:: ይኸውም ሙሽራዋ ከዘመዶቿ ቤት ትኖራለች፣ ባል ደግሞ ከገዛ ዘመዶቹ ጋር ይኖራል:: (ይህን በተመለከተ በምዕራፍ 9 በዝርዝር

እንመለከተዋለን)። ከሦስትና አምስት ዓመት በኋላ ሙሽራው ብዙውን ጊዜ ከእናት አባቱ ቤት አጠገብ ቤት ሠርቶ መኖሪያውን እዚያው ያደርጋል። በጣም የቅርብ ቤተሰብ የሆኑ በአንድ ላይ መኖር በአብዛኛው የተለመደ ነው፤ ሆኖም በጣም ሰፋ ባለመልኩ የአክስትና የአጐት ልጆች ከነልጆቻቸው ተሰባስበው በአንድ ላይ የመኖር ሁኔታም አለ። አንድ ግለሰብ በቤተሰብ ውስጥ በሚፈጠር ግጭት ወይም በኑሮ መዛባት ምክንያት በሁለት ቦታዎች መኖር የሚገደድበት ጊዜም ይኖራል። አዲስ ትዳር መሥራቾች እንደፍላጐታቸው በሚስትዮዋ ወላጆች ወይም ሌላ ዘመድ አጠገብ፣ ወይም ከአባቱ ሌላ ከሌላ ዘመድ አጠገብ ኑሮአቸውን ሊመሠርቱ ይችላሉ። በመሠረቱ የቅማንት ወንድ ልጆች የአባታቸውን መኖሪያ አካባቢ ሳይለቁ ይኖራሉ ቢባልም፣ በተግባር ሲታይ ግን ብዙ ጊዜ ከዚህ ውጭ በተለያዩ ቦታዎች መኖሪያ መመሥረታቸውን በግልጽ መረዳት ይቻላል።

ባለፉት መቶ ዓመታት ቅማንቶች የአባት መኖሪያን እንደሚያከብሩና የአባትን የዘር ግንድ ተከትለውም ትውልዳቸውን ይቆጥሩ እንደነበር ቢታወቅም አሁን ቀስ በቀስ አንድ ግለሰብ በሌሎች ቦታዎች ኑሮውን መመሥረት እንደሚችልና የዘር ሐረግንም በተመለከተ የእናትንና የአባቱን ሐረግ መምዘዝ ከተጀመረ ሰነባብቷል። ቀደም ብሎ እንደተገነዘብነዉ የአባት የዘር ግንድን መሠረት አድርጐ ሐረግ መምዘዙ ጉዳይ አሁንም በከፍተኛ ደረጃ በጐሣዎችና በዋና ክፋዮች ዘንድ ከሃይማኖት ጋር የተሳሰረው ማኅበራዊ አደረጃጀት እንደተጠበቀ ነው።

## የግራና ቀኝ የትውልድ አደረጃጀትና መሬት ይዞታ

አንዳንድ ማኅበራዊ ኃላፊነትን ለመወሰን እንዲረዳ የአባት የዘር ሐረግን ተከትሎ ትውልድን መቁጠር የነበረ ቢሆንም ባህላዊ ትብብርን ለማግኘትና የንብረት አወራረስን በተመለከተ የግራና ቀኝ የትውልድ ሐረግን መምዘዝ የተለመደ ነው። የመሬት ተካፋይ ለመሆን የእናትንና የአባትን ዘር መቁጠር ለምን እንደሚያስፈልግ ከዚህ ቀጥሎ እንረዳለን። የመሬት ተካፋይ ነኝ ለማለት የእናት ወይም የአባት የዘር ሐረግን እስከ አሥራ ስድስት ትውልድ ቅድመ-ቅድመ-አያት ወይም ከዚያ በላይ ቆጥሮ

መጀመሪያ መሬቱን ካረሰው ሰው ጋር ትውልዱን ካገናኘ በቂ ይሆናል።

ብዙ የቅማንት ወንዶች የሚኖሩት በአባታቸው የትውልድ ቦታ ነው። ዘር አቆጣጠራቸውም ይበልጥ የሚያዘነብለው የአባት የዘር ሐረግን ተከትሎ በመሆኑ አንድ ግለሰብ እርዳታና የሥራ ትብብር ሲያስፈልገው በመጀመሪያ በአካባቢው የሚገኙትን የአባቱን ዘመዶች ነው የሚጠይቀው። እቶ ረዳ የእርሻ ወበራ (ደቦ) ሲያስፈልጋቸው መጀመሪያ ልጆቻቸውን፣ ቀጥሎ ወንድሞቻቸውን ከነልጆቻቸው በመጨረሻም የአጎቶቻቸውን ልጆች ያስተባብራሉ። ሥራው ብዙና ከባድ ከሆነ ደግሞ ያላቸውን ዘመድ አዝማድ፣ ማኅበርተኞቻቸውን፣ በጡት ልጅነትና በአበልጅነት የሚታወቁትንና ጎረቤቶቻቸውን እንዲተባበሩዋቸው ይጠይቃሉ።

አንድ ግለሰብ ባለው የሥራ ጫና መጠን እንዳስፈላጊነቱ ከሁለቱ የዝምድና ሐረጎች ጋር ያለውን ግንኙነት ያጠብቃል ወይም ያላላል። ከሁለቱም ወገኖች የጉልበት እርዳታና አንዳንዴም ጠብ ሲያጋጥመው እንዲያግዙት ያደርጋል። ከሩቅ አካባቢ የሚገኙ የእናትና የአባት ወገኖች በሠርግ፣ በተዝካርና በቀብር ሥነሥርዓቶች ከመገኘት በስተቀር በጉልበት ሥራ እንዲረዱ አይጠበቅም፣ ነገር ግን የእናትም ሆነ የአባት ወገኖች አንድ ዘመዳቸው በሰው እጅ ቢጠፋ ደሙን መበቀል፣ የራሳቸው ወገን ነፍስ ሲያጠፋ ደግሞ የደም ካሣ መዋጮ መክፈል ይኖርባቸዋል። አንድ ቅማንት ዘመዱ የሆነ ሰው ደም ካለበት የሟች ወገኖች ዘር ቆጥረው ሊገድሉት ወይም ጉዳት ሊያደርሱበት ስለሚችሉ በዚህ ረገድ መተባበር ይኖርበታል።

በመሬት አጠቃቀም ብዙ ጊዜ ግጭትና ክስ ሊነሣ ይችላል። ይህ ሁኔታ የሚከሰተው አንድ ተወላጅ ነኝ የሚል ሰው ለብዙ ዘመን ተዳፍኖ የቆየውን የርስት ጥያቄ የዘር ሐረግ በመምዘዝ ማረስ አለብኝ ብሎ ሲነሣ ነው። በመሠረቱ አንድ ግለሰብ መሬት የግል ንብረቱ ሳይሆን ከዘመዶቹ ጋር ተወላጅ የሆነበትን መሬት እየተካፈለ ወይም ከሌላ መሰሉ ከሆነ ሰው መሬት እየተከራየ በማረስ አለባ-ገለባውን ብቻ ያገኛል። አባወራው ሲሞት ሚስቱ በጋራ ያፈሩትን ተንቀሳቃሽ ንብረት ግማሹን አንስታ ሌላውን ግማሽ ለልጆቿ ትተዋለች። የመሬት

ባለመብትነት የሚወሰነው በደም ትስስር ስለሆነ ሚስት ባሏ ይዞት የነበረውን የመሬት ባለመብትነት መጠየቅ አትችልም። ለስሙ ያህል ቢሆንም ወንድና ሴት ልጆች አባታቸው በሁለቱም የዘር ሐረግ ይዞት የነበረውንም ሆኖ ገና ወደፊት በተወላጅነቱ ሊጠይቅ የሚችለውን መሬት የመጠየቅ ሁሉም እኩል መብት አላቸው።

አንድ አባወራ ሚስቱ ያላትን የመሬት ተጠቃሚነት መብት ጥያቄ ከዘመዶቿ ጋር ቅራኔ ሊያስነሣበት ስለሚችል ብዙ ጊዜ ጥያቄውን ከማንሳት ይቆጠባል። ይህን መብት ብዙውን ጊዜ ለወንድሞቿ ይተወዋል። ነገር ግን መሬቱ ከሚያርሰው እርሻ አጠገብ ወይም ኩታ-ገጠም ከሆነ የተዳፈነውን የመሬት ጥያቄ ሊቀሰቅሰው ይችላል። ለምሳሌ ያህል አቶ ረዳ የወይዘሮ አዳነች ወላጆች ከሚቆጣጠሩት ትናንሽ ቁራሽ መሬቶችን በዚህ ዓይነት መብት ተጠቅመው ያርሳሉ። ቅማንቶች በተወላጅነት ያገኙትንና ወደፊት የይገባኛል ጥያቄ ሊያነሱበት የሚችሉትን መሬት «ርስት» ይሉታል። «ርስት» ነፃ ይዞታ ማለት ሲሆን ተቃራኒው «ጉልት» (ጭሰኝነት) የሚለው ነው። ሌላው አለባ-ገለባውን ብቻ ለመጠቀም የሚያስችል ርስት ደግሞ በሌሎች ማኅበረሰብ የሚገኝ ለስሙ ያህል «ርስት» የሚባል ነገር ግን ጥያቄውን ለማስፈፀም ፈጽሞ ከማይቻልበት ደረጃ ላይ የደረሰ መሬት ነው። አንድ ቅማንት ገበሬ በእንደዚህ ባለ መሬት ለመጠቀምና እርሻውንም በቤቱ አካባቢ ለማሰባሰብና ለማጠናከር ሲፈልግ ይህን መሰል መሬት በጭሰኝነትም ቢሆን ይይዛል። በዚህ ሁኔታ በኩታ-ገጠም የሚያገኘውን መሬት ለሌላ ሰው ማከራየት የሚችል ቢሆንም ይዞታውን ግን በውርስ ሊያስተላልፍ አይችልም።

በከርከርና በጭልጋ በአንዳንድ ቦታዎች ገበሬዎች ለሚጠቀሙበት ርስት «አሥራት» እየተባለ የሚታወቀውን ግብር ይከፍላሉ። እስከ ቅርብ ጊዜ ድረስ የገዥው መደብ ሹማምንት ግብሩን ይሰበስቡ ነበር። አሁን ግን «ፈረሰኛ» እየተባሉ በሚጠሩ ዝቅተኛ ሹማምንት ተቆጣጣሪነት ግብሩ ገቢ የሚሆነው በቀጥታ ለብሔራዊው መንግሥት የገንዘብ ሚኒስቴር ነው። ፈረሰኞች ደግሞ የጪው ግብር የሚባለውን ለራሳቸው ይሰበስባሉ። እስከ ቅርብ ጊዜ ድረስ አሥራትና የጪው ግብር በእህል፣ በማር፣ በአሞሌ ጨውና በሌሎች ውጤቶች ይከፈል እንደነበር ቢታወቅም፣ በአሁኑ ወቅት ክፍያው በኢትዮጵያ ብር ተተክቷል። ዛሬ እያንዳንዱ ገበሬ የትምህርትና የጤና ታክስም መክፈል

ግዴታው ነው። እ.ኤ.አ. በ1965 ዓ.ም. ከመላው ክርክር ከልዩ ልዩ ዓይነት ግብሮች የተሰበሰበው የኢትዮጵያ ብር 6381 ነበር።

በሌላ አካባቢ የሚኖሩ የቅማንት ኅብረተሰቦች አሥራት አይከፍሉም። ነገር ግን «አምሾ» እየተባለ የሚታወቀውን ከፍተኛ ግብር ለባላባታዊ የጉልት አስተዳዳሪ ይከፍላሉ። በጦርነት ጊዜ ላሳዩት ጀብዱና በታማኝነታቸው የተሾሙት የባላባታዊው የገዥ መደብ አባላት በአንድም ሆነ ከዚያም በላይ በሆኑ ማኅበረሰቦች ላይ የተለያየ ሥልጣን ይኖራቸዋል። ግብር ይሰበስባሉ፣ የዳኝነት ሥራ ይሠራሉ፣ እንዲሁም እርሻቸውን በሕዝቡ በኩዳድ ያሳርሳሉ። በአውሮጳ የባላባታዊ አገዛዝ ሥርዓት ተንሠራፍቶ በነበረበት ወቅት እንደነበረው የሥልጣን ተዋረድ ዓይነት በኢትዮጵያም የሚሰጡ ማዕረጎች አሉ። እነዚህም እንደ ሥልጣን ቅደም ተከተል ከላይ ወደታች፡-

ንጉሠ ነገሥት
ንጉሥ
ራስ
ደጃዝማች
ፊታውራሪ
ቀኛዝማች
ግራዝማች ይባላሉ።

ሌሎች በሥልጣን ደረጃ መሠረት ያልተቀመጡ የሹመት መጠሪያዎች፡-

| | |
|---|---|
| ልዑል | ገዥ |
| ባላምባራስ | ፈረሰኛ |
| ሻለቃ | መቶ አለቃ |
| ባሻ | አምሣ አለቃ |
| በጅሮንድ | አሥር አለቃ |
| አዛዥ | ጭቃ ሹም |
| ሻምበል | |

የተባሉ ናቸው።

እንደነዚህ ዓይነት የሹመት መጠሪያዎች ሊወረሱም ላይወረሱም ይችላሉ፣ እንዲያውም አንድ ባለማዕረግ ታማኝነቱን ሲያጓድል ወይም የገዥው ጠንካራ ደጋፊ ካልሆነ የሹመት መጠ

ሪያውን ሊገፊፍ ይችላል፡፡ አንዳንድ ጊዜም ከፍተኛው የባላባት ገዥ በሥሩ ሌሎች ንዑስ የባላባት ገዥዎችን ሊመድብ ይችላል፡፡

ከርከር ከ1880ዎቹ ዓ.ም. በፊት ጉልት ነበረች፡፡ ሆኖም በአፄ ዮሐንስ አራተኛ ዘመን መንግሥት ክርስትናን በግድ እንዲቀበሉ ሲገደዱ ከርከር ጉልትነትዋ ቀርቶ የቅማንቶች ርስት ሆናለች፡፡ ከሁለተኛው የዓለም ጦርነት ወዲህ ብሔራዊው መንግሥት ዘመናዊ እየሆነ በመምጣቱ ነባሮቹ ባለባታዊ ገዥዎች አሁንም ያሉ ቢሆንም አዳዲስ እንዲሾሙ ማድረጉ ግን ቀርቷል፡፡ ጉልታዊው ሥርዓት እየፈራረሰ ለባላባታዊ ገዥዎች መገበሩ ቀርቶ አሁን አሥራት በቀጥታ ለማዕከላዊ መንግሥት ገቢ እየተደረገ ነው፡፡

## የቅማንት የዝምድና ስም አጠራር

ጥልፍልፍ የሆነው የቅማንት የዝምድና ሠንሰለት በኅብረተሰቡ ዘንድ የታወቀ ደረጃ ያላቸው ስያሜዎች አሉት፡፡ የሰው ዘር ማኅበራዊና ባህላዊ ጉዳይ አጥኝዎች (አንትሮፖሎጂስቶች) ከጥንት ጀምሮ በልዩ ልዩ ምክንያቶች ስለ ዝምድና ስያሜ ትንተና ያደረጉት አለበቂ ምክንያት አልነበረም፡፡ እነዚህን የዝምድና ስያሜዎችና የዘመዳሞችን እርስ በእርስ ግንኙነት በማጥናት፣ ፍፁም ነው ተብሎ የተገመተውን የሰው ባሕርይና በተግባር ከሚረጋገጠው (ዕውነተኛው) የሰው ባሕርይ ጋር ለማመዛዘን የሚያስችላቸው መሠረታዊ ጉዳይ በመሆኑ ነው፡፡ ለምሳሌ በቅማንቶች ዘንድ አራት የተለያዩ ዓይነት የወንድ ዘመዶች በአባት ትውልድ «አግ» (አጐት) ተብለው ይታወቃሉ፡፡ (መግለጫ ቁጥር ሦስትን ይመልከቱ፡፡) ሁሉም «አግ» (አጐት) ተብለው የተሰጡት ስያሜዎች በመሠረተ ሃሣብ ደረጃ እኩል ማኅበራዊ ሥፍራ አላቸው ይባላል፡፡ ነገር ግን በተግባር ላይ ሲታይ አንድ ሰው በእናቱ ወንድምና እና በእናቱ እኅት ባል ሁለቱ «አግ» (አጐት) ተብለው ቢሰየሙም የሁለቱን የዘር ሐረጐች መሠረት አድርጐ የርስት ተወላጅ ነኝ ማለት አይቻልም፡፡ «አግ» (አጐቶች) እየተባሉ የሚጠሩት የአባት ወንድሞች በባሕሪያቸው ከሌሎች «አግ» (አጐቶች) በጣም የተለዩ ናቸው፡፡ ይህም የሆነበት ምክንያት ቀደም ብለን እንደተመለከትነው ሁሉ ብዙውን ጊዜ አንድ ለዕለት ተዕለት ችግሩ እርዳታ የሚጠየቀውና ግንኙነት

የሚያደርገው ከአባቱ የቅርብ የዘር ሐረግ ካላቸው ጋር በመሆኑ ነው:: በማመዛዝን የሚደረግ የዝምድና ስያሜ ጥናት በተጨማሪ በሁለት ወይም ከዚያ በላይ ስለሆኑ ሕዝቦች ያለውን ታሪካዊ ግንኙነት ትክክለኛነት ወይም ትክክለኛ አለመሆኑን ለማረጋገጥ ይጠቅማል:: በተጨማሪም የቃላትን ትርጉምና የሰብአዊ ግንዛቤን መርምሮ ለመረዳት እንዲያስችላቸው የሰው ዘር አጥኝ ምሁራን የዝምድና ስያሜዎችን በሚገባ ያጠናሉ::

በሊዊስ ሄንሪ ሞርጋን ተሻሽሎና አድጐ በ19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን በግንባር ቀደም በወጣው ዝርዝር አጠናን ስልት መሠረት የቅማንት የዝምድና ስያሜ ሥርዓት ጥሩ መግለጫ ሲሆን፣ የአንድ ትውልድ አካል የሆኑና የተለያየ የዘር ሐረግ ያላቸው ዘመዳሞች በስያሜ ረገድ ከዘር ሐረግ ዝምድና ጋር አይደበላለቅም::



መግለጫ ቁጥር 3

የቅማንት የዝምድና ስያሜና ከአባት የዘር ክፋይ አባልነት

| ዝምድና | የቅማንት ስያሜ የፈላሻ ስያሜ | አማርኛ ስያሜ | የአባት ክፋይ የራስ | አባልነት ተቃራኒው |
|---|---|---|---|---|
| የአባት አባት | አን | እሚታ | X | |
| የአባት እናት | ታን | እሚታ | | X |
| የእናት አባት | አን | እሚታ | | X |
| የእናት እናት | ታን | እሚታ | X | |
| አባት | አባ | አባት | X | |
| እናት | ጋና | እናት | | X |
| የአባት ወንድም/የአባት እህት | አግ፣ተር | አጐት/አክስት | X | |
| የእናት ወንድም/የእናት እህት | አግ፣ተር | አጐት/አክስት | | X |
| የአባት ወንድም ሚስት/የአባት እህት ባል | ተር አግ | የጐት ሚስት/ያክስት ባል | | X |
| የእናት ወንድም ሚስት/የእናት እህት ባል | አግተ ተር | ያክስት ባል/የጐት ሚስት | X | |
| የሚስት አባት | አንሸን | አማት | | X |
| የሚስት እናት | ታንሸን | አማት | X | |
| ወንድም፣ እህት | ባን፣ ሻን | ወንድም፣እህት | X | |
| ሚስት | ዋና | ሚስት | | X |
| የአባት ወንድም ወንድ ልጅ/የአባት ወንድም ሴት ልጅ | አግሁራ | ያጐት ልጅ | X | |
| የአባት እኅት ወንድ ልጅ/የአባት እኅት ሴት ልጅ | ተርሁራ | ያክስት ልጅ | | X |
| የሚስት ወንድም/የሚስት እኅት | አንሸን/ዋርሳ | አማች/ዋርሳ | | X |
| የሚስት ወንድም ሚስት/የሚስት እህት ባል | ወርሳ/አንሸን | ኢጋቡንይ | X | |
| ወንድ ልጅ/ሴት ልጅ | ሁራ | ልጅ | X | |
| የወንድም ወንድ ልጅ፣ የወንድም ሴት ልጅ | ባናሁራ | የወንድም ልጅ(ወንድ/ሴት) | X | |
| የእኅት ወንድ ልጅ/የእኅት ሴት ልጅ | ሻናሁራ | የእኅት ልጅ(ወንድ/ሴት) | | X |
| የልጅ ሚስት(ወንድ)/የሴት ልጅ ባል | ዕርጉ/አንሸን | ምራት/አማች | | X |
| የሚስት ወንድም ወንድ ልጅ/የሚስት ወንድም ሴት ልጅ | አንሻሁራ | ያማች ልጅ | | X |
| የሚስት እኅት ወንድ ልጅ/የሚስት ወንድም ሴት ልጅ | ዋርሳይሁራ | የዋርሳ ልጅ | X | |
| የወንድ ልጅ ወንድ ልጅ/የወንድ ልጅ ሴት ልጅ | ሁራይሂራ | የልጅ ልጅ (ወንድ/ሴት) | X | |
| የሴት ልጅ ወንድ ልጅ/ የሴት ልጅ ሴት ልጅ | ሁራይሂራ | የልጅ ልጅ (ወንድ/ሴት) | | X |
| ባል (ሴቷ ስትናገር) | ገርዋ | ባል | | |
| የእናት ወንድም ወንድ ልጅ/የእናት ወንድም ሴት ልጅ | አግሁራ | ያጐት ልጅ | | X |
| የእናት እኅት ወንድ ልጅ/የእናት እኅት ሴት ልጅ | ተርሁራ | ያክስት ልጅ | | X |

በአብዛኛው ተግባራዊ በሆነው የስታየር ሙርዶክ ዝርዝር አጠናን ስልት በተለይም በወንድማማች ወይም በእኅትማማች ልጆች በኩል ያለውን የቅማንት የዝምድና አሰያየም የተመለከትን እንደሆነ የኤስኪሞዎች ዓይነት መሆኑን እንረዳለን:: «ያንኪዎቹም» (የኒውዮርክ ኗሪዎች) ቢሆኑ ልክ እንደኤስኪሞዎች ከሁለት ወይም ቁጥራቸው ከዚያም በላይ የሆነና በአንድ ወይም በሁለት ወላጆቻቸው የሚገናኙ ልጆች አሰያየማቸው ከአጐትና ከአክስት ልጆች የተለየ አይደለም:: ሮበርት ኤች ሉዊስ ባቀረበው የዝምድና አሰያየም ዝርዝር አወጣጥ ስልት የአሰያየም ሥርዓቱ በቀጥታ የዘር ትውልድ ሐረግን ተከትሎ ነው:: ይህም ማለት የአንድ ግለሰብ የእናት ወንድምና የአባት ወንድም በአጠራር ቀጥታ የትውልድ ሐረግ ካለው ዘመድ ለምሳሌ ከአባት ጋር የተለየ ሲሆን አንዱ ከሌላው ግን የተለየ አይደለም::

እዚህ ላይ መረዳት ያለብን ነገር ቢኖር የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪ የሆኑት ቅማንቶች የዝምድና አሰያየማቸው የሴም ቋንቋ ተናጋሪዎች ከሆኑት ከአማራ ሕዝብ ጋር ተመሳሳይነት ያለው መሆኑን ነው:: የማጠቀሙባቸው ቃላት ግን ፍፁም ልዩ ናቸው:: አገውኛ የሚናገሩት ፈላሻዎች የአባባል ቃናቸው ትንሽ ልዩነት ቢኖረውም የቅማንትን ስያሜዎች ነው የሚጠቀሙት:: አማርኛ ተናጋሪ ፈላሻዎች ደግሞ የአማራ የዝምድና አጠራር ቃላትን ይጠ ቀማሉ:: የዝምድናው አሰያየም ለእያንዳንዱ ምንም ይሁን ምን አንድ ቅማንት ከሁለት የዘር ግንድ ከአንዱ ወይም ከሌላው መሆኑን በሥነ ልቦናው ተቀርጾ ይኖራል:: የጋብቻ ጉዳይ ወይም የቀሳውስት ምርጫ ውይይት በሚነሳበት ጊዜ ይኸው ጉዳይ ሳይነሣ አይታለፍም:: የቅማንቱ የዘር አደረጃጀት በሁለት የተለያዩ ነገር ግን በጣም በተሳሰሩ ክብርና የታንቲ ከተባሉት የዘር ግንዶች ውጭ አይታይም:: በዚህ በታወቀው ጥንድ በሆነው የአደረጃጀት ሥርዓት አንድ ልጅ መጀመሪያ የሚያውቀው ነገር ቢኖር አባቱ «ክብር» ከሆነ እናቱ «የታንቲ» መሆኗን ነው::

## ማኅበራዊ (የፈጠራ) ዝምድና

**<u>የቃል ኪዳን አባትና ልጅ ግንኙነት</u>:: ክርስቲያን በሆኑ ቅማንቶች ዘንድ የክርስትና አባትና ወይም እናትነት የበለጠ የታወቀ ቢሆንም በአረማዊ-አሪታዊ ቅማንቶች ዘንድ «አንጉሁራ» ወይም «የጡት ልጅ» ተብሎ የሚታወቀው የቃልኪዳን አባትና**

ልጅ ግንኙነት አለ:: በዚህ ዓይነት የማኅበራዊ ዝምድና ቃል ኪዳን ለመተሳሰር የሚፈልጉ ሰዎች የጡት ልጆች ሊሆኑ ይችላሉ:: ብዙ ሰዎች ይህን ዓይነት ግንኙነት የሚፈልጉት በተለይ በአካባቢያቸው በደም የተሳሰሩ ትርብ ዘመዶች የሌላቸውና መሬትና ሀብት ሳይኖራቸው ሲቀር ነው:: ሀብታም ሆነው ብዙ ቤተሰብ የሌላቸው ደግሞ የወገን ድጋፍና ጉልበት ለማግኘትና እንዲሁም ቀባሪ ላለማጣት ሲሉ የጡት ወላጆች ይሆናሉ::

አንድ ለአካለ መጠን የደረሰ ሰው የጡት አባት ሲፈልግ በሀብት ረገድ ቢያንስ መካከለኛ ደረጃ ላይ የሚገኙትን ባልና ሚስት ይመርጣል:: ዕድሜው ለአካለ መጠን ካልደረሰ ደግሞ ሌሎች ሰዎች ይመርጡለታል:: በዚህ መልክ ነበር ስድስት ዓመት እድሜ ያለው ዘውዱ አራት ሴት ልጆችና ምንም ወንድ ልጅ የሌለው አዮ የተባለውን ቃልቻ ጡት የጠባው::

ከእለታት አንድ ቀን ጠዋት አየሩ ደስ የሚልና ቀዝቃዛ በነበረበት የበጋው ወቅት በተካሄደው ሥነሥርዓት አዮና ባለቤቱ አውራ ጣታቸውን በማር ቀብተው ጡት በማስመሰል ዘውዱ እንዲጠባ ተደርጐ ሁለቱም እናትና አባቱ መሆናቸውን ለጡት ልጃቸው ቃል ኪዳን ገቡለት:: ከዚህ በኋላ አዮ የጡት አባት («እንጉአባ»)፣ ሚስቱ ደግሞ የጡት እናት («እንጉጋና») ሲሆኑ ዘውዱ ደግሞ የጡት ልጅ («እንጉሁራ») ተብሎ ታወቀ:: ከዚያች ዕለት ጀምሮ ከሕይወት ፍፃሜም በኋላ ቢሆን ይህ የቃል ኪዳን አፀፋዊ የሆነ የወላጅና ልጅ ግንኙነት ይኖራል ማለት ነው::

አንዲት የጡት ልጅ ያላገባች ከሆነች የጡት አባትና እናት ማጫውን ይችላሉ፣ ሠርጉንም ይደግሱላታል:: ወንድ ከሆነ ደግሞ እጅ መንሻውን የጡት ወላጆች ይከፍላሉ:: የጡት ልጅ «እውነተኛ» (የተፈጥሮ) እናትና አባት ከሌለው ወይም ድሆች ከሆኑ ከጡት ወላጆች ጋር እየሠራ ይኖራል:: በመጨረሻም ልክ እንደ እውነተኛ ልጆቻቸው መሬትና ንብረት የመካፈል መብቱ የተጠበቀ ይሆናል:: የጡት ልጁ ከማኅበራዊ ወላጆቹ ጋር አብሮ የማይኖር ከሆነ ግንኙነቱ በጣም ቅርብና የጠበቀ ይሆናል:: የጡት አባት ወይም እናት ከሞቱ የጡት ልጅ የቀብር ሥነሥርዓታቸው እንዲፈፀም ያደርጋል፣ የሙት ዓመት እንዲከብርና ተዝካርም እንዲወጣ ማድረግ አለበት:: እነዚህ

ሥነሥርዓቶች ሟችን ወደ ገነት እንዲያልፍ ያስችለዋል ተብለው ስለሚገመቱ አስፈላጊነታቸው መረዳት አያዳግትም።

የጡት ወላጅነት በበጌምድር በሚገኙ አማራዎች ዘንድ የታወቀ ቢሆንም ብዙ የተለመደ አይደለም። ከዚህ ይልቅ «አበልጅ» እየተባለ የሚታወቀው «የክርስትና አባት» እና «የክርስትና እናትነት» በአማራውም ሆነ በክርስቲያን ቅማንቶች ዘንድ በአብዛኛዎቹ የታወቀ ነው። አንድ ሕፃን ልጅ በክርስትና ሃይማኖት በሚጠመቅበት ቀን የክርስትና አባቱና እናቱ ልጁን እንደ ልጃቸው እንዲያዩት ቃል ኪዳን ይገባሉ። ይህ ቃል ኪዳን በመሠረቱ የጡት አባትና ልጅ ካላቸው ግንኙነት በጣም የላላና ቃልኪዳኑም ይህን ያህል የሚጠበቅ አይደለም።

የቃልኪዳን ወንድማማችነት። በቅማንቶች ዘንድ የታወቀው ሌላው ዓይነት የማኅበራዊ ዝምድና «ሚዜ» እየተባለ የሚጠራው ነው። ሚዜ የቃል ኪዳን ወንድምና እህታማችነት ማለት ሲሆን ቁጥራቸውም በርከት ያለ ሊሆን ይችላል። (ምዕራፍ ዘጠኝ ላይ ይመልከቱ።) የሚዜዎች መሠረት የሚባለው ጋብቻ በሚፈፀምበት ጊዜ ነው። ምንግዜም ቢሆን የወንድ ሚዜዎች ወንዶች ሲሆኑ የሴት ሚዜ ሴቶች ቢሆኑም ይህን ያህል በማኅበራዊ እንቅስቃሴአቸው በኩል ብዙ ትኩረት የሚሰጥበት አይደለም። ሚዜዎች አንድ ዓይነት ፆታ እንዲሆኑ የሚለው ደንብ በአሠራር ታሽሮ እናገኘዋለን። ይኸውም የወንድ ሚዜዎች ከሙሽራዋም የወንድምና የእህታማችነት ቃልኪዳን ከሠርጉ በፊት ሲገባቡ ስለምናይ ነው። ሰውዬው ካገባ በኋላ የሚዜዎች ቁጥር ሊጨምርና ሊቀንስ ቢችልም አዲሶቹ ከሚስቱ ጋር የፈጠሩ ዝምድና ቃልኪዳን አይገቡም። ሚዜዎች የሥጋ ዝምድናቸው ከሙሽራው ሰባት ትውልድ መራራቅ ይኖርበታል።

ማንኛውም ግለሰብ የራሱ የሆኑ ሚዜዎች ያሉት ሲሆን የሁሉም የጋራ ግንኙነት ከሙሽራው ጋር ያላቸው ማኅበራዊ ወንድማማችነት ብቻ ነው። ሚዜዎች ከሙሽራው ጋር የሚኖራቸው ግንኙነት የተወሰነ ስለሆነ ሁሉም በአንድ ቀንና በአንድ ጊዜ አይገናኙም። ሆኖም አንዳንድ ሚዜዎች ለሌላ ሰው ሚዜ ለመሆን ስለሚችሉ ግንኙነታቸው እየሠፋ ሄዶ በፈቃደኝነት የጋራ ማኅበር እስከ መመሥረት ሊደርሱ ይችላሉ።

በዘመዳሞች መካከል የተከለከለ የግብረ-ሥጋ ግንኙነትም በእነዚህ የቃልኪዳን ወንድማማቾችም የማይደረግ ጸያፍ ነገር ነው። (በበጌምድር የሚገኙ አማራዎች ሚዜዎች ያላቸው ሲሆን ከፍ ብሎ የተገለፀው በሚዜዎች የተለያዩ ፆታዎች የሚደረገው ግንኙነት ግን የተከለከለ አይደለም።) ስለሆነም የሁለት ሚዜዎች ልጆች አንዱ ከሌላው ጋር አይጋባም፣ ወይም አንዱ ከሌላው የሥጋ ዝምድና ሰባት ትውልድ ርቆ መገኘት ይኖርበታል። በተጨማሪም አንድ ግለሰብ ሚዜ የሆነለትን ሰው ዘመድ ሰባት ቤት ካልሞላ በስተቀር አያገባም ነበር። በአሁኑ ጊዜ ግን ይህ ሁኔታ በተግባር ተሻሽሎ በሶስትና በአራት ቤት መጋባት ተጀምሯል።

በሚዜነት የተሳሰሩ ሁለት ሰዎች የሚኖራቸው ግዴታና ኃላፊነት ከሥጋ ዘመዶች ብዙም የተለየ አይደለም።። በደቦ ይተባበራሉ፣ ግጭት ሲያጋጥም አንዱ ለሌላው ያብራል፣ የተለያዩ የሠርግና የተዝካር ዝግጅት በሚኖራቸው ጊዜ በአፀፋው የሚመለስ መደጋገፍ እንደአስፈላጊነቱ አለ።

<u>የቃል ኪዳን ጓደኛ</u>። በመሃላ የተሳሰረ ጓደኝነት የተለመደ ነው። በተለይ ደግሞ «የቃል ኪዳን» ጓደኞች ካሉ እርስ በእርሳቸው ይደጋገፋሉ፣ የጋራ ወይም የግል ችግሮቻቸውን ማንም ሳይሰማ ተወያይተው መፍትሔ ያስገኛሉ። የቃል ኪዳን ጓደኞች እነሱ ብቻ የሚጠቀሙበት፣ እርስ በርሳቸው የሚጠራሩበትና ፍቅራቸውን የሚገልጹበት ልዩ የቁልምጫ ስም አላቸው። ይህ ዓይነቱ የቃል ኪዳን ጓደኛነት በአብዛኛው በሥጋ ዝምድና፣ በፈጠራ ዝምድና ወይም የአንድ ማኅበር አባል በመሆን የሚጠናከር ዝምድና አይደለም።

## ማኅበራዊ ትስስር

ማኅበር ወይም አልፎ አልፎ የባዕዳን ቡድን ተቋም እየተባሉ የሚታወቁት የሚመሠረቱት የሥጋ ዝምድና ስንስለት ተዳክሞና ተበጣጥሶ በሚገኘው በሠለጠኑት አገሮች የሚገኙ ሲሆን አብዛኛውን ማኅበራዊ እንቅስቃሴአቸውን በእነዚህ ተቋሞች አማካይነት ያካሂዳሉ። አንድ «ያንኪ» (የኒው ዮርክ ኗሪ) በሠራተኛ ማኅበር ይታቀፋል፣ ወይም የአንድ ቤተክርስቲያን ወይም የአንድ የስፖርት ቡድን አባል ይሆናል። በሌላ በኩል ደግሞ በፖሊስ ተቋም፣ በእሳት አደጋና በጤና ድርጅት ደኅንነቱ እየተጠበቀ

ይኖራል። እንደቅማንት ባሉ የገበሬ ኀብረተሰቦችም ይህን የመሳሰሉ ማኅበሮች በተጨማሪ አሉአቸው። በማንኛውም ኅብረተሰብ እንደ ማኅበር ሲመሠረት ውስብስብነቱ ታስቦበት ነው። አብዛኛዎቹ ማኅበራት አባላት የሚመረጡበትን ወይም የሚመለመሉበትን ዝርዝር መስፈርት በማስቀመጥ በተዘዋዋሪ መንገድ ዘመዳሞች የሆኑትን ቡድን አባላት ቁጥር ለመገደብ የሚያስችል ስልት አላቸው። ለምሳሌ ከቅማንቶች ራቅ ብለው የሚኖሩት የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪ አረሞ ጐረቤቶቻቸው «ገዳ» ተብሎ የሚታወቅ የማኅበረሰብ አደረጃጀት ሥርዓት አላቸው። በዚህ ሥርዓት ኀብረተሰቡ በየስምንት ዓመት የዕድሜ ልዩነት ክልል ተደራጅተው በደረጃ የተለዩ ልጆች፣ አረኞች፣ ወታደሮች መሪዎችና አዛውንቶች ተብለው እንደሚመደቡ የታወቀ ነው። ሌሎች ሕዝቦች ደግሞ ሁለቱን ፆታዎች መሠረት በማድረግ የሴቶች ማኅበር፣ የወንዶች ማኅበር እየተባሉ የሚታወቁትና በአንዳንድ ኋላቀር ኀብረተሰቦች ውስጥ በሕቡዕ የሚቋቋሙት ድርጅቶች ምሳሌዎች ናቸው።

አብዛኛውን ጊዜ በቃል በሚደረጉ ኮንትራቶችና ስምምነቶች የተደራጁ ማኅበራት በተለይ በቅማንቱ ዓለም፣ በአጠቃላይ ደግሞ በመላው ዓለም የታወቁ ናቸው። እነዚህን የመሳሰሉ በቃል ስምምነቶች የተደራጁ ማኅበራት ሁሉም ነገር በአባላት በጐ ፈቃድ በዓላትን በአንድ ላይ ሆኖ ለማክበርና የእያንዳንዱን አባል ፍላጐት ለማርካት የተቋቋሙ ቢሆንም፣ አንድ አዲስ አባል በቃል ውል ከታሠረ በኋላ ከአባልነት የሚወጣበት መንገድ የጠበበ ይሆናል፣ መልቀቅም ያስቸግረዋል። አንድ ቅማንት በመሠረቱ ማኅበሩን በፈቃዱ መልቀቅ ይችላል ቢባልም ከለቀቀ በኋላ ጓደኛ አልባ እንደሚሆን ይረዳዋል። ይህም በመሆኑ የጋራ የሥራ ትብብር የነበራቸው የአንድ ማኅበር አባላት እዮን «ያ ዲቃላ ተጠቅሞብን ወጣ» እያሉ ማኅበርተኞቹ ጠላ እየጠጡ በየቦታው መሳለቂያና ስሙ እንዲጠፋ ባላደረጉት ነበር። ሁኔታው ሊፈጠር የቻለው እዮ ቃል አባይ በመሆን ከዚህ ቀደም የአንድ ማኅበር አባል ሆኖ በደቦ ብዙ ሥራ ከተሠራለት በኋላ ብድሩን ሳይመልስ በመውጣቱ ነበር። በሌላ መልኩ ደግሞ በአንዳንድ አጋጣሚዎች አንዳንድ አባላት ተገቢውን ሥነምግባር ካጓደሉ ከአባልነት የሚወገዱበት ሁኔታም አለ።

ማኅበርና ማኅበርተኞቹ። ማኅበር በቅማንቶችና በአማራው ኅብረተሰቦች አባላት በበጐ ፈቃደኛነት ይመሠረታሉ። በመሠረቱ የአባላት ብዛት አሥራ ሁለት እንዲሆን ቢፈለግም ከዚያም በላይ ሊሆን ይችላል። አንድ አባል «ማኅበርተኛ» ተብሎ የሚጠራ ሲሆን በተጨማሪ ማኅበርተኞች በሥጋና በማኅበራዊ ዝምድና የተሳሰሩ ሊሆኑ ይችላሉ። አንዳንድ ማኅበሮች የወንዶችና የሴቶች ተብለው ሊለዩ ቢችሉም በየወሩ በሚደረጉ ድግሶች የሁለቱ ፆታዎች ባለቤቶች ሊገኙበት ይችላሉ። በአብዛኛው ግን የወንዶች ማኅበር ከሴቶች የበለጠ ከፍተኛ ግምት ይሰጠዋል።

በተመሳሳይ የዕድሜ ክልል የሚገኙ ሰዎች ተሰባስበው ማኅበር የሚመሠርቱ ቢሆንም በጊዜ ሂደት የአባልነት ሁኔታ ሊለወጥ ይችላል። የማኅበር አባል መሆን አስደሳች፣ ከጓደኛ ጋር ተሰባስቦ በመብላትና በመጠጣት የሚያዝናና ለቤት ሥራና ለእርሻ ደቦ ጠቃሚ ነው። ከዚህም በላይ አንዱ አባል ጠብ ሲያጋጥመው ለመርዳት የሚያስችልና ከስም ሲመሠረት ዋስ በመሆን የሚያስተጋግዝ በአጠቃላይ ማኅበራዊ ተሳትፎን የሚያጠናክርበት ነው። አባላት የእርሻ በሬዎችንና ዕቃ በመዋዋስ፣ የእህል ዘርና ገንዘብ በመበዳደር በማኅበራቸው አማካይነት ይረዳዳሉ። ከዚህም በስተቀር አንድ አባል ሠርግና ተዝካር እንዲሁም ሌሎች መንፈሳዊ ሥነሥርዓቶች ሲኖረው አባላት ከሚሰጡት የጉልበት አገልግሎት በተጨማሪ የምግብ ዕርዳታ ያደርጋሉ። «ብድር በምድር!» የአባላቱ ቁልፍ መፈክር ሲሆን። አንድ አባል ይህን መሥፈርት በሚገባ ካላሟላ በመጀመሪያ ማስጠንቀቂያ ተሰጥቶች ካልተሻሻለ ደግሞ ከማኅበሩ ይወገዳል።

የሴቶች ማኅበር በወንዶች ዓይነት የተደራጀ ቢሆንም ይህን ያህል በኢኮኖሚም ሆነ በፍትሕ ረገድ የሚጫወተው ሚና ጉልቶ የማይታይና የደቦ ሥራ ምልልስም እምብዛም የማይታሰብበት ነው። የሴቶች ማኅበር መሠረታዊ ዓላማ ያላቸው የትብብር በጐ ፍላጐት ለመግለጽ ያህል ነው። ስብሰባቸው የሚካሄደው በወር ውስጥ በተለያዩ ቀናት ሆኖ ጊዜያቸውን የሚያሳልፉት ጥጥ በመፍተል፣ ስፌት በመስፋትና ወሬ በመጫወት ነው።

በየወሩ አንድ ሐሙስ ቀን በዓለ-እግዚአብሔር (የምዝግና በዓል) በሚከበርበትና ገባርሁ በሚታወስበት ሐሙስ ዕለት ቅማንቶች ትልቁንና የታወቀውን የማኅበራት ስብሰባ ያካሂዳሉ።

ይህ ስብሰባ የሚካሄደው በአረማዊ-ኦሪታዊ እምነት ተከታዮች ባሉበት ኀብረተሰቦች ነው። ስለእነዚህ ማኅበራት ቀደም ብሎ ስለ አዛውንቶች ሸንጎ በተነሣበት ጊዜ የተገለጸ ሲሆን እስከ 1950ዎቹ ዓ.ም. ከሠላሣና ከዚያም በላይ አባላት የነበሯቸው ቢሆንም በአሁኑ ወቅት ቁጥራቸው ተመናምኗል። መደበኛ የሆነው የአዛውንቶች ሸንጎ ስብሰባ የሚደረገው የምዝማና በዓል በሚከበርበት ዕለት በጥዋት ቀደም ብሎ ነው። የእነዚህ ትላልቅ ማኅበራት አባላት የአንድ ወይም ከዚያም በላይ የንዑስ ማኅበራት አባል ለመሆን ይችላሉ። ስብሰባቸውም የአረማዊ-ኦሪታዊ ባሕላዊ ጀግኖች በሚታወሱበት ቀን ይሆናል። ክርስቲያን የሆኑት ትማንቶች ግን ማኅበራቸው በወር አንድ ወይም ሁለት ዕሑድ ቀን ይሰበሰባል። በዚያም ምክንያት ማሕበራቸው «ሰንበቴ» (የዕሑድ ማኅበር) የሚለው ተጨማሪ ስያሜ ተሰጥቶታል።

# ምዕራፍ ስምንት

## ዓመታዊ ኤኮኖሚያዊና ሃይማኖታዊ ጥረት-ግረት::

አንድ የቅማንት ገበሬ የሚያመርተውን ሰብልና የሚያረባቸውን እንስሳት ለቤተሰቡ የኑሮ መሠረት የሚያደርገው ብቻ ሳይሆን ከዚሁ አትርፎ ለመንግሥት ግብር፣ ለሃይማኖታዊና ለቤተሰብ በዓላት ድግስና ሥነሥርዓቶች ይጠቀምበታል:: እንዲሁም አስፈላጊ ለሆኑ አገልግሎቶች ለውጥ ማግኛና በቀጣዩ ዓመት የተሻለ ምርትና የከብት እርባታ ለማግኘት እንዲያስችለው ለዘርና ለማንኛውም ችግር መጠባበቂያ ይይዛል::

የምግብ ምርትን ለማግኘት ለዘመናት ያካበተውን የሥራ ልምድና እንዲሁም መለኮታዊ በሆኑ ክስተቶችም በመተማመን መሬት ፀጋዋን እንድትለግሰው ይጥራል፣ ይግራል:: መለኮታዊ ክስተቶች ዓመታዊውን የኢኮኖሚ እንቅስቃሴ የሚቆጣጠሩ፣ እነዚህ ዓይነት ሁኔታዎች ከግለሰቡ ጥረት ጋር የተሳሰሩ መሆኑንና ሁለቱንም ዓይነት ክስተቶች በትክክል ለይተው ስለምንነታቸው ቅማንቶች ያውቃሉ:: ለምሳሌ ካልታሰበውና ከማይታይ በሕዝብና በሰብል ላይ ይደርሳል ብለው ለሚገምቱት መቅሰፍትና አደጋ ወምበሩ ስለስብሐት (ልምላሜ) የሚያደረገው ሥርዓተ-ቅዳሴ እንደዋስትና ስለሚወሰድ ሥነሥርዓቱ ሳይፈፀም አንድ ገበሬ ዘር መዝራት አይጀምርም:: ስለዚህ ገበሬው አስፈላጊና በቂ የሆነ የተመጣጠነ ዝናብ እንዲዘንብ በሚደረገው ሥርዓተ-ጸሎት ይካፈላል:: ነገር ግን ወገብ አጉባጭ የሆነውን እርሻ ማረስ፣ ጠንክሮ ማረም፣ በአጥንት ውስጥ የሚገባውን የክረምት ብርድ ተቋቁሞ መሥራት፣ በበጋ ወራትም መስኖ ማጠጣትና ወቅቱን ጠብቆ በስልት አጥሩን ማጠባበቅ የእራሱ የግል ጥረት እንጂ በተዓምር የሚሠራለት አለመሆኑን አጥብቆ ይገነዘባል::

የቅማንቶች የቴክኖሎጅ ዕድገትና የቤተ ሙከራ ልምድ በቂ ባለመሆኑ በተፈጥሮ ምክንያት የሚከሰቱትን ጥቃቅን ጭንቀቶችን መቆጣጠር ስለማያቅታቸው መለኮታዊ ሁኔታዎች ከአካባቢው አደጋ እንዲጠብቁአቸው ይማፀናሉ:: ስለዚህም በአንድ በኩል የበግ መንጋ ሰብላቸውን እንዳያበላሽ ዙሪያውን በአጥር እንዲታጠርና በጐችንም እንዲቆጣጠር ዱላ የያዘ እረኛ

ያሠማራሉ፤ በሌላ በኩል ደግሞ ሰብሉ ካልታሰበ የአንበጣ መንጋ ወረራ ወይም ከሰደድ እሳት እንዲጠበቅ ተሳውስቱ ጸሎት እንዲያደርጉላቸው ይማፀናሉ።

## ምርት በቅማንት ኤኮኖሚ

የቅማንት ኤኮኖሚ ከሥረ-መሠረቱ የሚበሉ ሰብሎችን በማምረት ላይ የተመሠረተ ነው። ሙሉ ጊዜያቸውን በፖለቲካና በሃይማኖት ጉዳዮች ከሚያሳልፉት ወምበሩ እና በትርፍ ጊዜያቸው የእርሻ ሥራ እያከናወኑ በቅስና እና በቢሮ ሥራ ከተጠመዱት የመንግሥት ሠራተኞች በስተቀር ማንኛውም ቅማንት የሙሉ ጊዜ ሥራው ግብርና ነው።

እርሻ። እንደሌሎች የቅማንት ወንዶች ሁሉ አቶ ረዳና ልጆቻቸው ሞፈርና ቀንበር ከማረሻ ጋር አዋደው በማቀነባበር በየዕለቱ ሁለት በሬዎች በመጥመድ መሬቱን በማረስ አለሳልሰው ለዘር ዝግጁ ያደርጋሉ። ከየካቲት ወር ወይም ከዚህ ትንሽ ቀደም ብሎ ጀምሮ ድንጋያማ የሆነውን መሬት በተለያየ አቅጣጫ ሦስት አራት ጊዜ ስምንት ኢንች (አጥቅ) በሚደርስ ጥልቀት ደጋግመው ሾሩ እስኪጠፋ ተገላብጦ ይታረሳል።

ከአንዱ ዓይነት የገብስ ዝርያ በስተቀር ሁሉም ሰብሎች በዝናቡ ወራት ከሰኔ እስከ መስከረም ባለው ጊዜ ውስጥ ነው የሚዘሩት። (መግለጫ ቁጥር አራትን ይመልከቱ) ትላልቅ ሰዎችና ወንዶች ልጆች አንዳንድ ጊዜም በትላልቅ ሴቶችና ልጃገረዶች እየተረዱ ጥራጥሬና የቅባት እንሎችን በመበተን ይዘራሉ፤ ነገር ግን እንደ ኑግና ቀይ ሽንኩርት፣ ድንችና ዱባ የመሳሰሉትን በእጃቸው ነው የሚተክሉት። የተዘራው ዘር እንዲሸፈን እንደገና መሬቱ ይታረሳል። የተሻለ ምርት ለማግኘት በምርጥ ዘር አይጠቀሙም፣ መሬት ሲያስክ የሰብሉ ዓይነት ይለወጣል እንጂ ብዙውን ጊዜ መሬት እንደገና እንዲደልብ ለማድረግ አይተውም።

የአቶ ረዳ ቤተሰብ ወንዶችም ሆኑ ሴቶች መኮትኮቻ በመያዝ ወይም በእጃቸው አረም ማረም የተለመደ ነው። በቅማንት አካባቢ የከብቶች ፍግ በአብዛኛው በማገዶነት ስለሚጠቀሙ በት ለማዳበሪያነት እንዲሆን የማድረጉ ልምድ የላቸውም። ከዚህም በስተቀር በዝናብ ውሃ ብቻ መጠቀም እንጂ በመስኖ

ብዙም አይገለገሉም፡ ነገር ግን በተለይ በጣም የታወቀውን ጤፍ ለመዝራት ብዙ ውሃ የጠጣ መሬት (ጨፌበሬ) ስለሚያስፈልግ በአካባቢው ካለ ኩሬ ወይም ትንሽ ወንዝ ጠልፈው መስኖ ያስገባሉ። ከመኸር ወቅት ውጭ ነጭ ሽንኩርት፣ ቀይ ሽንኩርትና በርበሬ የመሳሰሉት አታክልት የተተከሉባቸውን ቦታዎች በመስኖ ውሃ ማጠጣትም አልፎ አልፎ የተለመደ ነው። አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ ረግረጋማ እርሻዎችን ሾር ወይም ትንሽ ቦይ በመቅደድ ውሃው ተንጣሎ እንዲወጣ ያደርጋሉ።

ቅማንቶች የእርሻ ቦታዎቻቸውን አጭር የድንጋይ ካብ በመገንባት ወይም የግራርና የኢጋም አጥር በማጠር ከጉረቤት ገበሬዎች እርሻ ይከልላሉ። በተጨማሪም ዲቦች፣ ሾሮችና አልፎ አልፎ የተተከሉ ድንጋዮች የወሰን መለያ ይሆናሉ። እህሉ በቅሎ ማደግ ሲጀምር እንስሳት ገብተው እንዳያጠፉት የግራርና የኢጋም አጥር መከላከያ ማድረግ የተለመደ ነው።

እህልና ጥራጥሬ እንዲሁም የቅባት እህሎችን አዝመራ የመከወን ሥራ ለወንዶች በአብዛኛው የተተወ ቢሆንም፣ አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ ሴቶች እንዲረዱ ይደረጋል። በመኸር አሰባሰቡ ሂደት መጀመሪያ እህሉ ታጭዶ ይሰበሰብና በአንድ ላይ ይከመራል። ከዚያም ክብ የሆነ ዙሪያውን በትናንሽ ድንጋይ የተከበበ በእበትና በጭቃ የተለቀለቀ ስፋቱ ከዘጠኝ እስከ አሥራ ሁለት ጫማ የሚሆን አውድማ ይዘጋጃል። የእንጨት መንሽ በመጠቀም እህሉ በአውድማው ላይ ከተጣለ በኋላ አፋቸውን የተለጐሙ በሬዎችን ዙሪያውን በእህሉ ላይ በማስሄድ ፍሬው ከገለባው እንዲለይ ይደረጋል። የቅባት ሰብል የሆኑት ኑግ፣ ተልባና ሰናፍጭ ግን ፍሬውን ከገለባውና ከአገዳው ለመለየት እንደታሠረ አውድማው ላይ ተጥሎ በደህና ዱላ ይወቃል። ከዚያም ላዳ፣ መንሽና እንቅብ በመጠቀም ፍሬው ከእብቁና ከገለባው ከተለየ በኋላ በስልቻ ተሞልቶ በአህያ እየተጫነ ለክምችት ወደ ቤት ይወሰዳል።

የጥንቱ የቅማንት የጓሮ እርሻ አስተራረስ ዘዴ ሳይጠፋ አሁንም በአንዳንድ ቦታዎች መኖሩን ማየት ይቻላል። በበሬ መታረስ የማይችሉ ዳገታማ ወይም ገደላማ በሆኑ ቦታዎች ላይ የሚገኝ መሬት ደኑ በመጀመሪያ ይመነጠርና በእሳት እንዲጋይ ተደርጐ በዓመዱ የዳበረው መሬት በመቆፈሪያ ተቆፍሮ እህሉ ይዘራል። (እዚህ ላይ መኮትኮቻ ወይም መቆፈሪያ ኋላ-ቀር

ለሆነው የጓሮ አትክልት እርሻ መገልገያ መሆኑን፣ ሞፈርና ቀንበር ግን እየተሻሻለ የመጣው የእርሻ መሣሪያ መሆኑን እንገነዘባለን::) «ወጀድ» እየተባለ በሚጠራው የጓሮ አታክልት በሚተከልበትና በሚዘራበት ቦታ ላይ ደግሞ ሴቶችና ወንዶች አሁንም በመኮትኮቻ ይጠቀማሉ:: በእነዚህ የጓሮ አታክልት ቦታዎች ዝሬዎች ከሠፋፊ እርሻዎቻቸው ከሚያገኙት ምርት በተጨማሪ ለምግባቸው መደጎሚያ የሚሆኑ ልዩ ልዩ ሰብሎችንና አትክልቶችን ያለማሉ::

እንስሳት እርባታ:: ከብት ማርባት እንደ እርሻው ብዙ ትኩረት አይሰጠውም:: ሆኖም «ዜቡ» የተባሉ የከብት ዝርያዎች በጣም ተፈላጊ ሲሆኑ በሥጋቸውና በወተታቸው የሚጠቀሙ ከመሆኑም በላይ የእርሻ በሬዎችንም የሚያገኙት ከነዚህ ከብቶች ነው:: ጥገት ላሞችን ማለብ የወንዶች ተግባር ቢሆንም ሴቶችም አንዳንድ ጊዜ ያልባሉ:: ከላምና በሬ ቀጥሎ በተፈላጊነት በሁለተኛ ደረጃ የሚገኙት በግና ፍየል ናቸው:: እነዚህ የቤት እንስሳት ሥጋቸው፣ ፀጉራቸውና ቆዳቸው አገልግሎለት ላይ ይውላል፣ በወተታቸው ግን እምብዛም አይጠቀሙም:: በአረታዊው የአመጋገብ ሥርዓተ-ሕግ መሠረት ስለሚመሩ ቅማንቶች የእሣማ ሥጋና በጅብ ተነክሶ የረከሰ የከብት ሥጋ አይበሉም:: ከዚህም በስተቀር ቤታቸውን እንዲጠብቁ ውሾችን፣ በአይጠ-መጐጥ እንዳይጠቁ ድመቶችን ተንከባክበው ይይዛሉ:: ማንኛውም ቤተሰብ ብዙ ዶሮዎች በቤቱ ውስጥ ያረባል፣ እንዲሁም የባሕል ቀፎዎችን በመስቀል በመጠኑም ቢሆን የማር ምርት ያገኛሉ::

<u>አደንና ፍራፍሬ ለቀማ</u>:: በአሁኑ ጊዜ የሚታደኑ የዱር እንስሳት በአብዛኛው ስለሌሉ አደን እስከዚህ ተፈላጊነት የለውም:: ዓሣ ሞልቶአል፣ ነገር ግን መብላት በባሕላቸው የተከለከለ ነው:: አነስተኛ የሆኑ ወፍ ዘራሽ ለምግብ የሚያገለግሉ ፍራፍሬዎችና ቅመማ ቅመም ከጫካ ይለቅማሉ:: ለቤት ቁሳቁስ ማሥሪያ የሚሆን ስንደዶና ዘንባባ፣ ለልብስ ማጠቢያ የሚሆን እንዶድ፣ እንዲሁም ለማቅለሚያና ለመድኀኒት መቀመሚያ የሚያገለግሉ የተለያዩ እፅዋትን ከጫካ ለቃቅሞ መጠቀም የተለመደ ነው::



ዋሊ ዳቫ የተባለው ቦታ በጣም ዳገታማ ስለሆነ በሬ ጠምዶ ማረስ ስለሚያስቸግር የጥንቱን አስተራረስ ዘዴ በመጠቀም በመቆፈሪያ እየተቆፈረ እህል ሲዘራ::

<u>የእጅ ሥራ ውጤቶች</u>:: እንደ አማራው ኅብረተሰብ ሁለገብ ከሆነው ከእርሻው ሙያ በስተቀር በቅማንት ዘንድ ሌሎች የእጅ ሙያዎችን ማንቋሸሽ የተለመደ ነው:: በቅማንትና በአማራው ዘንድ ክብር ሊሰጣቸው ይገባል ተብሎ የሚታመንባቸው አራት

ሙያዎች፡- ግብርና፣ ውትድርና፣ የፖለቲካ መሪነትና ቅስና ናቸው:: እንዲያውም ቅማንትና አማራ የእጅ ጥበበኛነትን ከመጥላታቸው የተነሣ በጉዳዩ ላይ ውይይት ከተጀመረ ይህን የመሰለውን አባባል ይሠነዝራሉ፣ «የእጅ ጥበበኛ ከምታገቢ ይሻልሻል እንደበተ-ርቱስ ተናጋሪ»::

እንድም ቅማንት ለገበያ የሚውል የእጅ ሥራ ውጤት የማያመርት ቢሆንም ለቤቱ አገልግሎት ብቻ የሚሆኑትን ግን በጥሩ ሁኔታ ይሠራል:: ሴቶች ሞሰብ፣ እንቅብ፣ ሰፌድ፣ ቆለምሸሽ የመሳሰሉትን ይሠፋሉ፡ ወንዶች ደግሞ ከቃጫ ወይም ከእንስሳት ፀጉር ገመድ ይገምዳሉ፡ የድንጋይ ወፍጮ ከነመጁ አዘጋጅተው ይወቅራሉ:: ቤት በሚሠሩበት ጊዜ የአናጺ ሥራ፣ የሣር ክዳን ሥራ ያከናውናሉ:: ሞፈር፣ ቀንበርና ሌሎች የቤት ቁሳቁሶችን ማዘጋጀት የሥራ ድርሻቸው ነው:: አንድ ገበሬ የአናጺነት ችሎታው ከሌሎች ላቅ ብሎ የተገኘ እንደሆነ የሌሎች ሰዎችን ቤት በመሥራት በአፀፋው አንዳንድ ዕቃዎችን ወይም ለእርሻው የተወሰኑ ቀናት የጉልበት አገልግሎት ቤቱን ከሠራለት ሰው ያገኛል:: የብረታ ብረት መሣሪያዎችን ከፈላሻ ወንድ ቀጥቃጮች፣ የተለያዩ የሸክላ ውጤቶች ደግሞ ከፈላሻ ሸክላ ሠሪ ሴቶች በምትኩ የተለያዩ ዕቃዎችን በመስጠት ወይም በገንዘባቸው በመግዛት ያገኛሉ:: የቅማንት ሴት ለራሷ ልብስ የሚሆነውን ጥጥ በእንዝርት በመፍተል ልቃቂቱን ለፈላሻ ወይም ለእስላም ሸማኔ በማቅረብ ልብሱ ይሠራላታል:: በቆላ የሚገኙ ሴቶችም የሠሌን ምንጣፍ ማዘጋጀት ይችላሉ:: የቆዳ ውጤቶች ሲያስፈልጋቸው «አረብኛ» ከሚባሉ ፋቂዎች ይገዛሉ:: በነገራችን ላይ ፋቂዎች አማርኛ ተናጋሪ ሲሆኑ ለጋብቻ የተከለከሉና እንደሌላው አማራ የሚታዩ አይደሉም::

## በቅማንት ኤኮኖሚ የሀብት ስርጭት

ቅማንቶች ምርታቸውን የሚያሠራጩበት ሦስት ዓይነት ስልቶች አሏቸው:: እነዚህም ዕቃዎችንና አገልግሎቶችን መደበኛ በሆነ ገበያ በመለዋወጥ፣ መደበኛ ባልሆነ ሁኔታ ደግሞ ከገበያ ውጭ ልውውጥ በማድረግ፣ ከዓመት በዓል ጋር በተያያዘ ምክንያት መዋጮ ሰብስቦ እንደገና ተመልሰው በሚሰጡ አገልግሎቶች ለሁሉም በማዳረስና ብድር በመመላለስ የሚደረጉ ስርጭቶችን ያካትታል:: አብዛኛው ቅማንት ብዙውን ዓይነት

የንግድ ልውውጥ የሚያደርገው ሥራ በሚበዛባቸው ሞቅ ባሉት መደበኛ በሆኑት ገበያዎቻቸው ብቻ ሳይሆን ወደፊት እንደምንመለከተው ከዚያ ውጭ የንግድ ይዞት ሳይኖራቸው የእርስ በእርስ የዕቃ ልውውጥ በሚያደርጉባቸው ቦታዎች ጭምር ነው።

መደበኛ ገበያ። በቅማንት አካባቢ ትራንስፖርትና የመገናኛ መስመሮች ስላልተስፋፉ ለመገበያየት ምርጫቸው እዚያው በቅርብ በሚገኙ ገበያዎች ነው። በመደበኛውም ሆነ መደበኛ ባልሆነው ገበያ ግብይት የሚካሄደውና የዕቃና የአገልግሎት ዋጋዎች ልውውጥ የሚወሰነው በአቅርቦትና በፍላጎት ላይ ተመሥርቶ ነው። ገንዘብ መደበኛ በሆኑት ገበያዎች ዋና መገበያያ ሲሆን ሥርዓት ባልያዙት መደበኛ ባልሆኑ ገበያዎችም ቢሆን ይጠቀሙበታል። ዛሬ በኢትዮጵያ በወረቀት ገንዘብና በመዳብ ሳንቲሞች መጠቀም የተለመደ ሆኖአል። የሀገሪቱ ሕጋዊ ገንዘብ ባይሆንም በአሥራ ሰባተኛው ምዕተ ዓመትና ከዚያም ወዲህ በኦስትሪያ እየተቀረፀ ሲወጣ የነበረው የማሪያ ቴሬዛ ብር አሁንም በተግባር ላይ እየዋለ ነው። እንዲያውም በብርነቱ በጣም ተፈላጊነት ስላለው ብዙ ሰዎች ብሩን በመሰብሰብ ያከማቻሉ። ከዚህም በስተቀር በጥንታዊነቱ የንግድ መለዋወጫ በመሆን ይታወቅ የነበረው አሞሌ ጨው አገልግሎቱ ከአምሣ ዓመት በፊት ቢቋረጥም አልፎ አልፎ ለአንዳንድ ጥቃቅን አገልግሎቶች በተለይም ቀሳውስት ለሚፈጽሙት ሥርዓተ-ቅዳሴዎች በስጦታ መልክ ይሰጣቸዋል።

መደበኛው የገበያ ቀን በተወሰኑ ቀናትና ቦታ ይውላል። ገበያ በማይኖርበት ጊዜ የገበያ ቦታው በአብዛኛው ጠፍ መሬት ነው። ከአሥር ዓመታት በፊት የቅማንት ኅብረተሰብ ጠፍ በሆነ ቦታ ላይ በሳምንት አንድ ጊዜ የሚውል አንድ ገበያ፣ በአካባቢው በሚገኙ ጎረቤት የአማራ መንደሮች ደግሞ በየተራ የሚያገለግሉ ስድስት ገበያዎች ነበሩ። የድሮዎቹ በከርከር የሚገኙት ሁለት ገበያዎች በሚውሉበትን ቀናት ሰኞ ገበያና አርብ ገበያ ይባላሉ። በደቡብ ምዕራብ ከርከር ደግሞ ሮቢት እየተባለች የምትጠራው ገበያ ጭላ ውስጥ ትገኛለች። ቅዳሜ ገበያ ደግሞ በቅርባቸው በሚገኘው በጉንደር ከተማ ውስጥ በዕለተ ቅዳሜ ይውላል። ዛሬ የአስተዳደርና የገበያ ማዕከል የሆኑት አይከል፣ ሠራባና ትክል ድንጋይ የተባሉት ትናንሽ ከተሞች በሳምንት ስድስት ጊዜ አነስተኛ ግብይትና በሳምንት አንድ ወይም ሁለት ጊዜ ትልቅ

የገበያ ቀን ስለሚውል ነባሮቹ የቅማንት የገጠር ገበያዎች እየተረሱ መጥተዋል። በተጨማሪም ከቅማንቱ አካባቢ ውጭ አዲስ የአስተዳደርና የገበያ ማዕከሎች በመፈጠራቸው ሕዝቡ በእነዚህ እየተጠቀመ ነው። ከሁሉም የሚበልጠው ደግሞ በበጌምድርና ሰሜን ጠቅላይ ግዛት ዋና ከተማ ከ1600 ዓ.ም. ጀምሮ የተቋቋመው ታላቁ ቅዳሜ ገበያ ከመደበኛው ገበያ ቀን በተጨማሪ በየቀኑ አነስተኛ አገልግሎት የሚሰጥ ገበያ አለ።

ገጠሬው ቅማንት ወደ ገበያ የሚወጣው ከአመረተው ሰብል ከራሱ ፍጆታ ተርፎ የሚገኘውን ምርቱን ይዞ ነው። እሱ ማምረት የማይችለውን ነገር ግን ለኑሮው ደግሞ አስፈላጊ የሆኑትንና የጐደሉትን ለማሟላት ከሌላው ገበሬ ወይም ነጋዴ ጋር የምርት ልውውጥ ያደርጋል። አንዳንድ አገልግሎቶች ለምሳሌ ሞሰብ ወይም ቁና በቆዳ ለማስለበድ ወደ ገበያ መሄድም አለ። ብዙ ጊዜ ቅማንቶች የሚፈልጓቸው በአካባቢያቸው መመረት የማይችሉትን ለምሳሌ ጥጥ ከቆለኞች፣ አሞሌ ጨው ከደንከል በረሃ ሲመጣ ይለዋወጣሉ። እንዲሁም ለመሥራት የማይፈልጓቸውን ብረታ ብረት ከፈላሻዎች ይገዛሉ ወይም በለውጥ ያገኛሉ። በውጭ አገርም ሆነ በአገር ውስጥ በፋብሪካ የተመረቱ ዕቃዎች በአካባቢያቸው ባይገኙም በጠቅላይ ግዛቱ ዋና ከተማ ጐንደር ያገኛሉ። በጐንደር፣ በአዘዞ፣ በጐርጐራ ከተሞችና በሌሎች መንደሮች የሚገኙ ኢትዮጵያዊ ነጋዴዎች፣ የአረብ ጅምላ ነገዴዎች እና የተትረፈረፈ ምርት ያላቸው ገበሬዎች ናቸው የንግዱን ሥራ የሚያከናውኑት። በገጠር ከሚገኙ ገበያዎች ከአካባቢው ገበሬዎች ዕቃዎችን የሚገዙት ደግሞ በንግድ ላይ የተሰማሩ ተዘዋዋሪ ነጋዴዎች ናቸው።

ለወቅታዊ ወሬዎች ወደገበያ! ወደ ገበያ! ወደ ገበያዎች መሄድ ከልውውጥ በተጨማሪ ለቅማንቶች ሌላ ጠቃሚነት አለው። ከሁሉም በላይ ማኅበራዊ ግንኙነትን በኅብረተሰቡ ዘንድ ያጠናክራል። ገበያ ሲወርዱ ባል አግብተው ራቅ ወዳለ ቦታ የሄዱ ሴቶች በምንም ዓይነት በሌላ መንገድ ሊያገኙ የማይችሉትን ዕድል በመጠቀም በገበያው ቀን ከዘመዶቻቸው ጋር በመገናኘት ስለዘመድ አዝማድና ስለድሮ ጐረቤቶቻቸው ደኅንነት ተጠያይቀው ይረዳሉ፤ ይወያያሉ። ወዳጅና ዘመዳሞች ገበያ ወጥተው ዕቃ ለመግዛትም ሆነ ወይም ለመሸጥ በቂ ምክንያት ስላላቸው አንድ ቀን ሥራ ፈትቶ በገበያው በመገኘት

ስለቤታቸውና ስለእርሻቸው አዲስ ሁኔታዎች ካለ እርስ በርስ ሃሣብ ለሃሣብ መለዋወጥ የተለመደ ነው። ከቤቷ ወደ ገበያ የመጣች ሴት የያዘችውን ምርት ሸጠችም አልሸጠች ደንታ ባይሰጣትም ወደ ገበያ መሄድ ራሱ ለእሷ ትልቅ መንፈሷን የሚያድስ ትርዒት ነው። በአጠቃላይ የገበያ ቦታዎች ዘወትር የቅርብና የሩቁን ኅብረተሰብ እርስ በርሱ ፊት ለፊት እንዲገናኙ በማድረግ መንፈሳቸውና ጠባያቸው እንዲረጋጋ ይረዳቸዋል።

በገበያ ቦታዎች ኅብረተሰቡ አዲስና እንግዳ ነገሮችን ያያል፣ የዳምጣል፣ ይማራል። ከዚህም በስተቀር በመንግሥት የሚነገሩ መመሪያዎችና አዋጆችን ይሰማሉ። ሠላም ሰፍኖ ከተሞችና አካባቢው እንዲለማ ግብር መሰብሰብ እንዲቻልና ንግድ እንዲስፋፋ ለማበረታታት የገበያዎችን ደህንነት መጠበቅ ግዴታ ስለሆነ የመንግሥት ሹማምንትና ኃላፊዎች ከፍተኛ ጥረት ያደርጋሉ። የገበያዎችን ሁኔታ በማጥናትና በመቆጣጠር ሹማምንቱ የሕዝቡን የልብ ትርታ ማዳመጥም ይችላሉ።

መደበኛ ያልሆነ ግብይት (የእጋጣሚ ገበያ) የምንለው በሁለት ሰዎች መካከል ነጋዴም ሆነ ደላላ ጣልቃ ሳይገባባቸውና በገንዘብ ሳይጠቀሙ በማንኛውም ቦታና ሰዓት ዕቃ በዕቃ ልውውጥ የሚደረግበት ሁኔታ ነው። በአብዛኛው ልውውጥ የሚደረገው እኩል ዋጋ አላቸው ተብለው በሚገመቱ ሁለት ዕቃዎች መካከል ነው። የእንስሳት ልውውጥ ከመደረጉ በፊት የሁለቱ ከብቶች ዋጋ አስቀድሞ በማሪያ ቴሬዛ ብር ይተመንና ልዩነት ካለ ዝቅተኛ ግምት ያለው እንስሳ ይዞ የቀረበው ማካካሻ የሚሆን የተወሰነ ማሪያ ቴሬዛ ብር ይደበድባል (ይጨምራል)።

<u>መዋጮ መሰብሰብና ማሠራጨት</u>። በቅማንት ኅብረተሰብ ሦስተኛው ዓይነት የኢኮኖሚ ሥርጭት ስልት የሚከሰተው ደግሞ የቅማንት የሃይማኖትና የቤተሰብ ክብረ- በዓላት በሚከበሩበት ጊዜ ነው። ከበዓላት ጋር በተያያዙ ምክንያቶች ገንዘብ፣ መጠጥና የበሰለና ያልበሰለ መግብ በመዋጮ ተሰብስቦ እንደገና ተመልሶ የሚከፋፈልበት ሁኔታ አለ። ገበሬዎች ለመስዋዕት እና ለድግስ እንስሳትና እህል እንደየችሎታቸው ለወምበሩና ለቀሳውስቱ ያዋጡና ድግስ ተደግሶ ትንሽ ያዋጡም ሆነ ብዙ ያዋጡ በአንድ ላይ



መደበኛው ቅዳሜ ገበያ በጐንደር ከተማ ሲታይ፣ መሐል ላይ የሚታየው ትልቁ ዋርካ ዕድሜው ሦስት መቶ ዓመት ነው። የተተከለውም ከአድማስ ባሻገር በስተግራ የሚታየው የፋሲል ግንብ በ1600 ዓ.ም. መሐል ቅማንት አገር ላይ በተገነባበት ጊዜ ነበር።

እስኪጠግቡ ይመገባሉ፣ ይጠጣሉ:: በእንደዚህ ያለ ሁኔታ ሥጋ አግኝተው የማያውቁ አንዳንድ ምስኪን ገበሬዎች በዓመት የተወሰኑ ቀናት በክብረ-በዓላት ቀን ሥጋ የመብላት ዕድል ያጋጥማቸዋል ማለት ነው:: አንዳንድ ጊዜ በመዋጮ የሚደረጉ ድግሶች ዘመድ አዝማዶችንና የአንድ ማኀበር አባላትን ብቻ ሊመለከት ይችላል:: ለጉት መግቢያና ለተዝካር ተብሎ የሚደረገው መዋጮ ሥነሥርዓቱ ከሚመለከተው ቤተሰብ ይሰበሰብና ድግሱን የኅብረተሰቡ አባላት ይከፋፈሉታል:: በሃይማኖት ምክንያት ለድግስ የሚሰበሰበው መዋጮ ተመልሶ ለመላው ኅብረተሰብ ስለሚውል የቅማንቶችን የአንድነት ቃልኪዳን የሚያድስና የሚያጠናክር ከመሆኑም በላይ የባህል ድንበራቸው ተጥሶ በውስጣቸው ሌሎች ሠርገው እንዳይገቡ የሚያግድ ነው::

በእንካ-በእንካ (መተጋገዝ):: ቅማንቶች ቀላል ግምት የማይሰጠው የዕቃና የአገልግሎት ልውውጥ በእንካ-በእንካ ያደርጋሉ:: ይህም በጡት አባትና በጡት ልጅ መካከል በተደረገ ቃልኪዳን መሠረት የሚደረግ አፀፋዊ ምላሽ ወይም በአንድ ግለሰብና በሚዜዎቹ መካከል በደቦ መረዳዳት ወይም በአንድ ማኀበር አባላት መካከል በደቦ ቤት በመሥራት ረገድ መተጋገዝ ሊሆን ይችላል::

በእንካ-በእንካ የሚደረጉት የአገልግሎት ልውውጦች ዋጋቸውን ተምኖ ለማመዛዘን አስቸጋሪ ነው:: ለምሳሌ አንድ ቄስ ዘወትር የሚመግበውንና ጥሩ አገልግሎት የሚሰጠውን አንድ ገበሬ ሕዝቡ ከፍተኛ ምስጋናና ምርቃት እንዲሰጠው ተፅዕኖ ሊያደርግ ይችላል:: በሌላ መልክ ደግሞ ሁለት ቤተሰቦች እርስ በእርሳቸው ተራ በተራ ተጠራርተው በማያቋርጥ ሁኔታ ስጦታ መለዋወጥና መገባበዝ ይኖራል:: እንዲሁም አንድ ሀብታም ሰው ስሙን ለማስጠራት አስቦ በየጊዜው ሕዝቡን በመጋበዝ ሊያስደስት መሬቱን ለሚያርሱለት ደግሞ የተለዩ ከፍተኛ ስጦታ ሊያደርግ ይችላል:: በአጠቃላይ ስናየው አንዱ ለአንዱ በአፀፋው ወይም በእንካ በእንካ የሚያደርግለትን በሚዛን ላይ አስቀምጦ ማመዛዘን ያስቸግራል::

# የሥራና የዕረፍት ቀናት

ዕለታዊ ጥረት-ግረትና ዕለታዊ ደቦ:: ከሰንበት፣ ከምዝግና እና ከገባርሁ በዓላት በስተቀር በቅማንቶች ዘንድ ሁሉም ቀናት የሥራ ቀን ናቸው:: አቶ ረዳና ቤተሰቦቻቸው ሥራ የሚጀምሩት ከንጋት በፊት ቀደም ብሎ ነው:: ወይዘሮ አዳነች እንደተነሱ እንጨቱን አስተካክለው በምድጃው ላይ እሳቱን ያያይዛሉ:: እሳቱ ከጠፋ ትንሽ ቀዳዳ ባለው እንጨት ላይ ሌላ እንጨት በማፋጨት የሚወጣውን ትንሽ እሳት በደቃቅ ፍግ ማያያዝ ይችላሉ:: ነገር ግን ብዙ ጊዜ እሳት እንዳይጠፋ ጥንቃቄ ይደረጋል:: እሳቱ እንዳይጠፋ ወይዘሮ አዳነች ፍም ከአመዱ ውስጥ አዳፍነው ያስቀምጣሉ፣ ከጠፋም የልጅ ልጃቸውን ወደ ጐረቤት በመላክ የከሰል ፍም እንዲያመጡላቸው ያደርጋሉ:: ከዚያም ወይዘሮ አዳነችና ምራቶቻቸው ፀሐይና አልማዝ በቀን ሁለት ጊዜ የሚበሉትን ምግብ አዘጋጅተው ከባለቤቶቻቸው ጋር እና ሌላም ሰው ካለ በአንድ ላይ ሆነው ይመገባሉ::

ሴቶች ወደ እረኛ ቦታ ለሥራ መሄድ ያለባቸው ከሆነ ከመሄዳቸው በፊት አስፈላጊ የሆነውን የቤት ሥራ መሥራት ስላለባቸው ከሌሊቱ በ9 ሰዓት መነሣት ይኖርባቸዋል:: ወደ እርሻ ለሥራ የማይሄዱ ከሆነ ግን የማገዶ እንጨት በመልቀምና ትልቅ እንስራ ወይም ቅምጫና (ትልቅ ቅል) በመያዝ አጠገባቸው ወደአለ ምንጭ ወይም ወንዝ በመውረድ ውሃ በማመላለስ ጊዜአቸውን ያሳልፋሉ:: ውሃ ብዙ ጊዜ የማይጠጣ ሲሆን ዕቃ ለማጠብ፣ ምግብ ለማዘጋጀትና ጠላ (ሰላብ) ለመጥመቅ ይጠቀሙበታል:: ቤት መጽዳት፣ ሕፃናትን መያዝ፣ የጓሮ አታክልት መኮትኮት፣ የእጅ ሥራ መሥራትና እህል በወፍጮ መፍጨት የመሳሰሉት ለሴቶች የተተው ሌሎች ተግባሮች ናቸው::

በሬዎች በተለይ በክረምት ወራት ተለቀው ሣር መልቀም ስለማይችሉ አቶ ረዳ ከእንቅልፋቸው እንደተነሡ የመጀመሪያ ሥራቸው በሬዎቻቸው መኖ እንዲያገኙ ማድረግ ነው:: ከቤታቸው ሲወጡ ከምድጃው ከሚወጣው የባሕር ዛፍ ቅጠል ጭስ ከተሞላው የማለዳው ብርዳም አየር ጋር ይጋፈጣሉ:: በዚያን ጊዜ ላሞች መጮህና መንቀሳቀስ ይጀምራሉ፣ አውራ ዶሮውም ጩኸቱን ያስተጋባል:: አቶ ረዳና ሶስት ልጆቻቸው ቁርሳቸውን በልተው ወደየሥራቸው ይሠማራሉ:: የዕለቱ ተግባር በእርሻ ላይ ውሎ

ወይም ቤት መሥራት፣ ወይም ወደገበያ መሄድ ሊሆን ይችላል። አልፎ አልፎም እንደ አቶ ረዳ ያለ አዛውንት በሸንጎ ላይ በመገኘት የዳኝነት ሥራ መሥራትም ያጋጥመዋል።

ትንሽ አደግ ያሉ ወጣት ልጆች ቁርሳቸውን ትላላቅ ሰዎች ከበሉ በኋላ በተራቸው በልተው ወንዶች ከብቶችን ለማሠማራትና ለመጠበቅ ይወጣሉ፣ ልጃገረዶች ግን በጣም ትናንሽ ከሆኑት ልጆች ጋር በቤት ቀርተው እናቶቻቸውን በቤት ሥራ ይረዳሉ።

የወይዘሮ አዳነችን አብዛኛውን ጊዜ የሚፈጀው በጣም አስፈላጊ የሆነውን በየዕለቱ የሚበላውን ምግብ የማዘጋጀቱ ሥራ ነው። ምግቡ የሚቀቀለውና የሚጋገረው ሦስት ጉልቻ ባሉት የአሳት ምድጃ ላይ ነው። ሥጋ የሚበላው በሁለት ወይም ከዚያም በላይ በሆኑ ሣምንታት አንድ ጊዜ ብቻ ነው። ብዙ ጊዜ በዋና ምግቦች መካከል ቆሎና ንፍሮ ለመክሰስ ይቀርባል፣ አንዳንድ ጊዜም በቅመም የጣፈጠ ዳቦ መብላትም የተለመደ ነው። ዳቦው በምጉጉ (የሸክላ ምጣድ) ወይም በገበር ምጣድ ላይ ቃ ብሎ እንዲበስል ተደርጐ ይጋገራል። አቶ ረዳና ቤተሰቦቻቸው ዳቦ ብቻ በቂ አለመሆኑን በመገንዘብ በርካታ እህል በተለይም ገብስን ጠላ ለመጥመቅ አገልግሎት ያውሉታል። ለጠላው ማጣፈጫም የጌሾ ቅጠል ይጨመርበታል። ቡና ድሮ በቅማንት ኅብረተሰብ እንዳይጠጣ የተከለከለ የነበረ ቢሆንም በአሁኑ ጊዜ ግን ዋጋውም በመወደዱ ለአንዳንድ ክብር ለሚሰጣቸው የተለያዩ ቀናት ብቻ ይፈላል። ቡናን በጨው ወይም በማር ይጠጡታል፣ ወተት ደግሞ በተለይ ለሕፃናት ነው የሚሰጠው።

በቀን ሁለት ጊዜ ለሚቀርቡት ዋና ምግቦች (ምሣና እራት) በሚገባ ጣፍጦ በድስት የተሠራ ወጥ (ሳዌብ) እና እንጀራ (አራሀ) ይቀርባል። ወጡ በርበሬ የበዛበትና ብዙ ዓይነት ቅመማ ቅመም፣ ቅቤ፣ ዘይት፣ ሽንኩርት፣ አንዳንድ ጊዜም ሥጋ ታክሎበት በሸክላ ድስት ተጥዶ ተንተክትኮ ሲበስል ይወጣል። እንጀራው ደግሞ ብዙ ጊዜ የጤፍ፣ አልፎ አልፎም የገብስ ወይም የማሽላ ወይም የስንዴ፣ የበቆሎ ዱቄት ከተቦካ በኋላ ክብ በሆነ የሸክላ ምጣድ (ምጉጉ) ተጋግሮ ዓይናማ ሆኖ ይወጣል። በርካታ እንጀራ እንደ ጠረጴዛ በሚያገለግለው ሞሰብ ላይ ተደርድሮ ከቀረበ በኋላ እጅ የሚያስቆረጥመው ወጥ በላዩ ላይ ቀስ በቀስ እየተደረገ ይበላል።

አልፎ አልፋ ሲያጋጥም ለስላሳ ዓይብ ከመጡ ላይ እየተደረገ የሚበላበትም ጊዜ አለ:: አይቡ በዳቦም ሲበላ ጥሩ ነው::

ምሽት ላይ አቶ ረዳና ልጆቻቸው ከዕለታዊ ተግባራቸው ሲመለሱ የልጅ ልጆቻቸው ደግሞ ከብቶቻቸውን እየነዱ ወደ በረት ያስገባሉ:: ከዚያም ላሞች ከታለቡ በኋላ እራት ተበልቶ ጉልማሶቹ በእሳቱ መድኳ ዙሪያ እንደንብ በመሰፈር ጠላ እየጠጡ ስለውሎአቸው ያወካሉ:: በአጋጣሚ የመጣ እንግዳ ዘመድም ካለ አብሮ ይስተናገዳል:: በመጨረሻም የመኝታ ሰዓት ሲደርስ አቶ ረዳ ይተኛሉ፣ ሚስት ያገቡት ልጆቻቸውም ስለመሸ ወደየቤታቸው ስለሚሄዱ ሁሉም ነገር ፀጥ ረጭ ይላል:: ባልና ሚስት በአንድ ላይ የሚተኙ ሲሆን ትናንሽ ልጆቻቸውም አንዳንድ ጊዜ አብረዋቸው ይተኛሉ::

ሰንበት፣ የምዝግና እና የገባርሁ በዓላት:: «ሰንበት» ተብሎ የሚታወቀው ከአርብ ምሽት ጀምሮ እስከ ቅዳሜ ምሽት ያለው ጊዜ ነው:: የሃይማኖት ሥነሥርዓት በዚሁ ዕለት የሚካሄድ ባይሆንም በእርሻ ቦታዎችና በቤት ውስጥ ከሚሠሩ ሥራዎች በመታቀብ ሙሉ ቀኑን በዕረፍት ያሳልፉታል:: ለዚሁም አረማዊ-አሪት ሃይማኖት ተከታይ ቅማንቶች ብቻ ናቸው በከፊል የሰንበትን ሥነሥርዓት የሚጠብቁት:: ከባድ ሥራ አይሠሩም፣ ቀለል ያሉ ሥራዎችን ግን ያከናውናሉ::

በአብዛኛው ሰሜንና ማዕከላዊ ኢትዮጵያ የሚገኙ ሕዝቦች ሰንበትን እንደ ዕረፍት ቀን አድርገው የሚመለከቱት ባይሆንም የበዓል ቀን ነው ብለው የሚያከብሩት:: ቅማንቶች ከሌሎች ጉረቤቶቻቸው ጋር ያላቸው ልዩነት ቢኖር ሰንበትን እንደ ዕረፍት እንጅ እንደ በዓል ቀን አድርገው አለመውሰዳቸው ብቻ ሳይሆን ሌሎች በየወሩ የሚመጡትን የሃይማኖት ቀናትንም ዘወትር በዕረፍት ብቻ ስለሚያከብሩ ነው:: በወር አንድ ጊዜ ሐሙስ ቀን የምዝግና (የእግዚአብሔር) በዓል ሌላው ሐሙስ ደግሞ ጥንት ምናልባት እንደ አንድ ዝቅተኛ አምላክነት ይታይ ስለነበረው አሁን ደግሞ እንደ አንድ መልአክ በሚታወቀው ገባርሁ ስም ይከበራል:: ሁለቱም ቀኖች እንደሰንበት በዕረፍት ታስበው ይውላሉ:: በእነዚህ ቀናት በቅዱስ ድግናዎች የሚደረግ ሥነሥርዓት ባይኖርም ቅማንቶች ጸሎት ያደርጋሉ፣ የማኀበራት ስብሰባ ያካሂዳሉ፣ እንዲሁም በምዝግና እና በገባርሁ ስም

ለጉረቤቶች የጠላ ግብዣ ማድረግ የተለመደ ነው:: የእሬታውያን ስንበት ከሃይማኖታቸው ጋር ከመጨመሩ በፊት ምናልባት በወር ሁለት ወይም ከዚያ በላይ የሚሆኑ ሐሙስ ቀኖች የቅማንት የሃይማኖት የዕረፍት ቀኖች እንደነበሩ መገንዘብ ይቻላል::

ቅማንቶች ቅዱስ ናቸው ለሚሏቸው ከአካባቢያቸው ከሚገኙ ድግናዎች ጋር የሚታወቁትን ጥንታዊ ባህላዊ ጀግኖቻቸውን በየወሩ አንድ ወይም ከዚያ በላይ በሆነ የዕረፍት ቀን ያከብሯቸዋል:: ለእያንዳንዱ ባህላዊ ጀግና የአንድ ቀን በዓል የሚታሰብ ሲሆን የዕረፍት ቀኖች ብዛትም በኅብረተሰቡ አካባቢ ባሉት ቅዱስ ድግናዎች ብዛት መሠረት ይወሰናል:: እያንዳንዱ ኅብረተሰብ ቢያንስ አንድ ድግና ብቻ ሲኖረው ሌሎች ከዚያ በላይ ሊኖራቸው ይችላል:: በዓመት ውስጥ በየወሩ ከሚከሰቱት ዓመት በዓል አንደኛው ከሁሉም የላቀ ነው ተብሎ ስለሚወሰድ ለባህላዊ ጀግናው ክብር በስሙ በተሰየመው ድግና ልዩ ሥነሥርዓት ይካሄድለታል:: ለሌሎች የባህል ጀግኖች የዓመት በዓላት ቀን ግን ልዩ የክብረ በዓል ሥነሥርዓት ሳይካሄድ እንዲሁ በዕረፍት ቀን ብቻ ታስቦ ይውላል::

## ዓመታዊ የሥራና ሃይማኖታዊ እንቅስቃሴ ዑደት

የቅማንቶችን ዓመት በዓላት አከባበር ስንመረምር የኢኮኖሚና የሃይማኖታዊ እንቅስቃሴዎች አንዱ በሌላው ላይ ተደጋጋፊና የተሳሰሩ መሆናቸውን እንረዳለን:: ማንኛቸውም ኢትዮጵያዊ ገጠሬና የጉሣ አባላት አካባቢያቸውን በቴክኖሎጂ ለመቆጣጠር እንዲያግዛቸው በመለኮታዊ ኃይሎች የሚተማመኑ ቢሆንም፣ ቅማንቶችን ልዩ የሆነው የሃይማኖታቸው ባሕርይ በውጭ ከጉረቤቶቻቸው ተገልለው እንዲኖሩ፡ በውስጥ ደግሞ እርስ በርሳቸው በአንድ ላይ ተሳስረው እንዲኖሩ አድርጉአቸዋል:: የጸሎት ሥነሥርዓታቸውን በምስጢር በድግና ውስጥ የሚያካሂዱ በመሆናቸው በሌሎች በስሜናዊና ማዕከላዊ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ዘንድ ልዩ ስለሚያደርጋቸው አንዳንድ የተሳሳተና ተቀባይነት የሌለው ጭፍን ትርጉም በመስጠት «ከእንጨት የመጡ፡ ምስጢራዊ ዕምነት በጫካ የሚያካሂዱ» እያሉ ሃሜት የሚሰነዝሩ አይጠፉም::

ቀን መቁጠሪያ:: ቅማንቶች ወርንና ጨረቃን በአንድ ዓይነት ስያሜ «አረፋ» እያሉ ስለሚጠሩ ምናልባት ጥንት ጨረቃን ተከትሎ የሚደረግ የቀን አቆጣጠር ሥርዓት እንደነበራቸው የሚጠቁም ነው:: ከዚህም በስተቀር የከዋክብትን ዓመታዊ እንቅስቃሴና ስለጨረቃ ገታ አንዳንድ ግንዛቤ ቢኖራቸውም ስለኮከብ ቆጠራ ያላቸው ዕውቀት ውስን በመሆኑ ለዘመናዊ የቀን መቁጠሪያነት አይጠቀሙበትም:: ስለሆነም ክርስቲያን ኢትዮጵያውያን የሚጠቀሙበትን እያንዳንዱ ባለ30 ቀን 12 ወራትና ጳጉሜ ተብሎ ባለ አምስት ወይም በ4 ዓመት አንድ ጊዜ ስድስት ቀናት ያሉትን ተጨማሪ ወር የቀን አቆጣጠር ሥርዓት ይከተላሉ:: (መግለጫ ቁጥር አራትን ይመልከቱ):: ይህ አቆጣጠር ከጎርጎሪዎስ አቆጣጠር ሰባት ዓመት ወደኋላ የቀረ በመሆኑ እ.ኤ.አ. መስከረም 11ቀን 1965 ዓ.ም. በኢትዮጵያ አቆጣጠር መስከረም 1 ቀን 1958 ዓ.ም. ነበር:: ቅማንቶች ይህን አቆጣጠር ከአማራው በመውሰዳቸው የሚጠቀሙበት የወር ስያሜ አማርኛ ነው:: ሆኖም ለወቅቶች ስያሜ የቅማንትኛ ቃላትን ይጠቀማሉ:: እንደ አማራውና በመካከለኛው ምሥራቅ አካባቢ የሚኖሩት ሕዝቦች የመጀመሪያው የቀኑ ሰዓት ከንጋቱ ላይ ጀምሮ እስከ ፀሐይ ግባት ይደርሳል፡ ሌላው የሌሊቱ ቀጣይ ጊዜም እስከ ንጋቱ አስራ ሁለት ሰዓት ይደርሳል:: የቅማንት አገር (መሬት) ለምድር ወገብ ቅርብነት ስላለው የፀሐይ መውጫና መግቢያ ሰዓት በዓመት ውስጥ ብዙ ለውጥ አያሳይም:: ይህም በመሆኑ ከጥዋቱ አንድ ሰዓት ሁልጊዜ በሃያ አራት ሰዓት ዞሮ የሚደርሰው በተመሳሳይ ጊዜ ነው:: የቀኑን ግምታዊ ሰዓት የፀሐይን አቀማመጥ ተመልክተው ማወቅ ይችላሉ:: ይህን ሁኔታ በተመለከተ አቶ ረዳ በዚህ መልክ ዘወትር የቀኑን ሰዓት እቅጩን ሲነግሩኝ እደነቅ ነበር::

<u>የክብረ በዓላት መጀመር</u>:: የመጀመሪያው የኢትዮጵያ ክርስቲያን ዘመን አቆጣጠር የሚጀምረው በመስከረም ወር ቢሆንም የቅማንት ዓመታዊ ኃይማኖታዊ ሥነሥርዓት ዙር በሁለተኛው ወር ጥቅምት ላይ ይጀመራል:: በዚህም ምክንያት ዓመታዊ የክብረ- በዓላቸው የመጀመሪያው ዙር የመኸር ወቅት ከሚጀምርበት ከጥቅምት ወር ጀምሮ ነው:: በጥቅምት ወር መግቢያ የመጀመሪያ ማክሰኞ ዕለት ቅማንቶች የዓመት በዓል መክፈቻ ቀን «በዓለ-ቤዛ» የተባለውን የቅዱስ ድግና የበዓላት ሥነሥርዓት ማክበር ይጀምራሉ:: ይህ በዓል ከርከር በሚገኘው

ለምዝግና ድግና ላይ የሚከበር ሲሆን ስያሜው የምዝግና (የእግዚአብሔር) መታሰቢያ መሆኑን ያመለክታል።ተመሳሳይ በዓል ሐምሌ ላይ ማክሰኞ ዕለት ከባዱ የክረምት ወቅት እስኪያልፍ ድረስ የድግናዎች ዓመታዊ ክብር-በዓላት መዝጊያ ሥነሥርዓት የሆነው -በዓልዓለሜ- የተባለው ክብረ-በዓል ይከበራል። እዚህ ላይ ሊታወቅ የሚገባው በዓመት ሁለት ጊዜ የቅማንት ክብረ-በዓል የሚካሄድበት ድግና ክርክር የሚገኘው ጋለምዝግና (የእግዚአብሔር መታሰቢያ) ብቻ መሆኑ ነው።

በበዓላት መክፈቻና መዝጊያ ሥነሥርዓት ብዙ በጉች ለመስዋዕትነት እየታረዱ የሚከበሩ በዓላት ነበሩ። እስከ ቅርብ ጊዜ ድረስ የክርክር ቀሳውስት መደበኛውን የመክፈቻ ክብረ-በዓል ሳያከብሩ በማንኛውም ድግና ሥነሥርዓት መካሄድ አይቻልም ነበር። ይህም ሁኔታ በየትኛውም አካባቢ የሚገኝ የቅማንት ኅብረተሰብ የክርክሩ ወምበር የበላይ መሆኑን የሚያስገነዝብ ነው። የመጨረሻዎቹ ቀን በአረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖት ያምኑ የነበሩ ቅማንቶች ባለፉት ጥቂት ዓመታት ክርስትናን የተቀበሉ ቢሆንም ዛሬም በዓመት በዓል መክፈቻና መዝጊያ በዓላትን ስለሚያከብሩ፣ በሌላ አካባቢ ያሉት ቅማንቶች የበዓሉ አከባበር በራሳቸው ቀሳውስት እንደተጀመረላቸው በመቁጠር የተለመደውን የበዓላት አከባበር ዙር ይቀጥሉበታል። እዚህ ላይ መገንዘብ ያለብን በድግና ሳይከበሩ የቀሩ አንዳንድ ሥነሥርዓቶች በማንኛውም ጊዜ ሊካሄዱ የሚችሉ መሆኑን ነው።

አረማዊ-አሪታዊ ቅማንቶች ለተራ ጸሎት ሥነሥርዓት ካልሆነ በስተቀር በድግና ለሚካሄዱ ክብረ-በዓላት የሚከተሉትን ነገሮች መፈፀም አለባቸው። ቀሳውስት ለበዓሉ ዝግጅት በመጀመሪያ ለሦስት ተከታታይ ቀናት ከሰ ማኘክ ይኖርባቸዋል፡ በክብረ-በዓሉ ዋዜማ ቀሳውስቱም ሆኑ ማንኛውም ወደ ድግና የሚገባ ሰው ግብረ-ሥጋ ከመፈፀም መታቀብ አለበት፡ በመጨረሻም ቀሳውስቱ ሙሉ ንፅሕናቸውን ለማግኘት ሰውነታቸውን ታጥበው የፀዳ ልብስ መልበስ አለባቸው። ቀሳውስቱና ማንኛውም ተራ ሰው ከበዓሉ ዋዜማ ጀምሮ መስዋዕት የማድረጉ ሥነሥርዓት እስከሚጠናቀቅበት ማግሥት ድረስ ይፆማሉ።

አንድ ቀን አየሩ ቀዝቃዛ ውርጫማም በሆነበት በዓሉ በሚከበርበት ጥዋት አንድ ዝቅተኛ ቄስ በገና ይዞ ወደ ድግናው ገብቶ በገናውን ሲደረድር አየሩ በሙሉ በሙዚቃ ተሞላ፡፡ ሌላው ቄስ ደግሞ በአንድ ላይ የተደባለቀ ማርና ወተት በተባረከው ቅዱስ መሬትና ዛፎች ላይ ያርከፈክፍ ጀመር፡፡ ወምበሩ የተሰበሰበውን ቀሳውስትና ሕዝቡን እየመራ ድግናው መሐል ሲደርስ ተቀመጠ፡ ሌሎች ግን ዙሪያውን አጅበውት ቆሙ፡፡ ከዚያም በአዕዋፍት የተሞላው አልፎ አልፎም በዝንጀሮዎች የሚዘወተረው ድግና ከየአቅጣጫው በሚመጡ አረማዊ-አሪታዊ ቅማንቶች ተጥለቀለቀ፡፡ ድግናው ለተሰየመለት የባሕል ጀግና ሁለት ቄሶች ለአንድ ሰዓት ያህል ከጸለዩና ከተደሱ በኋላ የቅማንት ኅብረተሰብ ከአንዱ የጥንት ቅድመ-አያታቸው የባህል ጀግና ጋር ያላቸውን ቃል ኪዳን እንደገና ያድሳሉ፡ በእሱም አማካይነት በእርስ በርሳቸው መካከል ያለውን አንድነታቸውን ያጠናክራሉ፡፡ ቀሳውስቱና ወምበሩ ከለምለሙ ድግና የሚመጣውን የሚያውድ ጥሩ ሽታ ያለውን የግራር ሙጫ ዕጣን እያሸተቱ ወደ ዳር ሲወጡ፡ በድጋሚ ዝቅተኛው ቄስ በገናውን ያሰማ ጀመር፡ ከፍተኛው ቄስ ደግሞ ማር በመሬቱ ላይ አርከፈከፈ፡፡ በመጨረሻም ተሰብሳቢዎቹ ምርቃት ተቀብለው እንዲቀመጡ ተፈቀደላቸው፡፡ ነገር ግን ክርስቲያን ቅማንቶች «ከአሮጌው ሃይማኖት» ተገልለው ለብቻቸው ሲቀመጡ፣ ቀሳውስት ከሁሉም ተራ ሰው ተነጥለው ለብቻቸው ቦታቸውን ያዙ፡፡

አልፎ አልፎ የግዕዝ ቃላት የሚጨመሩ ቢሆንም ጸሎት፣ ቅዳሴና ምረቃው የሚደረገው በቅማንትኛ ነው፡፡ ቅማንቶች እንደሚሉት ለሥነሥርዓቱ የሚጠቀሙባቸው አንዳንድ ቃላት በጣም ጥንታዊ በመሆናቸውና በአሁኑ ጊዜ ለዕለታዊ ንግግር ስለማይጠቀሙባቸው ትርጉማቸውን ለማወቅ አዳጋች መሆኑን ይገልፃሉ፡፡

የሚቀጥለው የበዓሉ አከባበር ክፍል ለመስዋዕት ደም የማፍሰሱና ድግስ የመብላቱ ጉዳይ ነበር፡፡ ለመስዋዕት የተዘጋጁት እንስሳት ለሥነሥርዓቱ የበኩላቸውን አስተዋፅዖ ለማድረግ በደመ-ነፍስ በመጠባበቅ ላይ ናቸው፡፡ በድግናው አካባቢ ከሚኖሩ የኅብረተሰቡ አባላት በመዋጮ የቀረቡ ሲሆን ትልቁ ክብረ-በዓል በሚኖርበት ጊዜ በርካታ ጥንድ ቀሳውስትና ለመስዋዕት የተዘጋጁ በርካታ እንስሳት ይኖራሉ፡ እንዲሁም ብዙ ሕዝብ ይሰበሰባል፡፡




መግለጫ ቁጥር 4፣ የቅማንት ቀን መቁጠሪያና ዓመታዊ የሥራ ዑደት

እንደ ከብርዋና ካዳስቲ የመሳሰሉ ቅዱስ ድግናዎች አንድ ትልቅ ድንጋይ ወይም ትናንሽ የድንጋይ ክምር የመሰዋዕት መንበር ሊኖራቸው ይችላል። ነገር ግን በአብዛኞዎቹ ድግናዎች የመሰዋዕት እንስሳት የሚታረዱት መሬት ላይ ነው። እንስሳቱ በሚታረዱበት ጊዜ በዝቅተኛ ደረጃ የሚገኙ ቀሳውስት ዋናው ቄስ በሚባርክበት ጊዜ የእንስሳውን እግሮች ወጥረው ይይዛሉ። ከብቱ ታርዶ ደሙ ወደ መሬት ፈስሶ ካለቀ በኋላ ከፍተኛው ቄስ የኋላና የፊት እግሮቹን በሣሳ ቢላዋ ይሠነዝራል። ቀሳውስቱ ደሙን በጠላ ይታጠቡታል። ግማሹን ጠላ ጠጥተው ከፊሉን ደግሞ በደም በተጨማለቀው መሬት ላይ ያፈሱታል።

በአካባቢው ሕዝብ መዋጮ የተዘጋጀውን ምግብና መጠጥ በታረደው እንስሳ አጠገብ ሰዎቹ ሲያስቀምጡ በሰሜናዊ ማዕከላዊ ኢትዮጵያ በተለመደው ዓይነት «ዕልልታ» በማሰማት ነው። ከዚያም እንስሳውን ገፈው ሥጋውን በመቆራረጥ ጠና ያሉት ያረጡ ሴቶች ወጥ እንዲሠሩ ይደረግና ሕዝቡ ወጡን በእንጀራ ይመገባል፡ በተጨማሪም ጠላና ጠጅ ቢጋን ይወርድና እየተቀዳ ይጠጣል፡ ቀሳውስቱ ምርጥ ምርጥ የሆነውን ምግብ ተሰጥቷቸው ያማቸውን እንዲፈቱ ይደረጋል፡ በመጨረሻም የተረፈ ምግብና ጠላ ካለ ሕዝቡ ተከፋፍሎ ወደየቤቱ ይዞ ይሄዳል።

የመስክ ጥናቱን በማካሂድበት በጥቅምት ወር ውስጥ በየቀኑ የተዘራውን ሰብል አስተዳደግ እከታተል ነበር። አቶ ረዳና ልጆቻቸው በእርሻ ቦታቸውና በጓሮአቸው የተዘራውን ባለስድስት ረድፍ ገብስ፡ ጉመን፡ ተልባ፡ አተር፡ ባቄላና ሽንኩርት የመሳሰሉትን በጥሩ ሁኔታ እየደረሱላቸው ስለሆነ በኩራት እየተመለከቷቸው ነው። ሰብሎች አሽተው የመታጨጃ ጊዜያቸው እየተቃረበ ነው። በዚህ ወር እንደተለመደው አልፎ አልፎ ከሚንጠባጠበው ዝናብ በስተቀር ሰማዩ እየጠራ የክረምቱ ወቅት ኢየከተመ ይመስላል። ነገር ግን አቶ ረዳን ጨምሮ ኅብረተሰቡ ከባድ ዝናብ ከዘነበ የደረሰውን እህል ሊያወድምባቸው ስለሚችል ከተትር በኋላ የሚያንገብበውን ደመና በሥጋት ይመለከቱታል። ይህ መጥፎ አጋጣሚ እንዳይከሰት አባውንቶች የተስተካከለ ዝናብ እንዲሰጣቸው የአካባቢው ቀሳውስት የጸሎት ሥነሥርዓት እንዲያካሂዱላቸው ይማፀኗቸዋል።(በአሁኑ ወቅት በአንዳንድ አካባቢ የቄስ እጥረት ስላለ ይህንኑ ሥነሥርዓት የጥንቱን አፈታሪክ የሚያውቁ ክርስቲያን ቅማንቶች ያካሂዱላቸዋል።) ዘንድሮ

ከባድ ዝናብ ዘንቦ ሰብላቸውን ባለማበላሸቱ አቶ ረዳ ያሉበት ኅብረተሰብ የተደረገው በዓላዊ ሥነሥርዓት የተሳካ ሆኖላቸዋል።



ቀሳውስትና አዛውንቶች ከብት አርደው ሲያጠናቅቁ።

አረማዊ-አረታዊና ክርስቲያን ቅማንቶች የተስተካከለ ዝናብ እንዲዘንብላቸው በሚያደርጉት በዓላዊ ሥነሥርዓት በየፊናቸው ለሥነሥርዓቱ የአካባቢው ቆሲ በሚኖርበት ቦታ ላይ በቆሲው ስም ወይም ቅዱስ በሆኑት ባህላዊ ጀግኖች ስም በሚጠሩ ድግናዎች ሊሆን ይችላል:: ዝናቡ በጥቅምት ወር በጣም እየጠነከረ ከመጣ ሥርዓተ-ጸሎቶች በተደጋጋሚ ይደረጋሉ:: በተለይም የሚሳተፉት የክርስቲያን ቅማንቶችም ቁጥር ከፍ ይላል::

የአካባቢ ቅዱስ ድግናዎች ክብረ-በዓል:: በኅዳር ወር እንደተለመደው ጋራዎች ደማቅ አረንጓዴ ምንጣፍ የተጐናፀፉ ይመስላሉ:: ወንዞችም ጠርተው ፀሐይ ወርቃማ ነፀብራቋን በላያቸው ላይ ትፈነጥቃለች:: መሬቱ እየደረቀ ሲሄድ በላዩ ያለው ሰብል መጐምራት ጀምሯል:: ይህ ጊዜ የክረምቱ ወቅት ማለፉን የሚያበስር ነው:: ከዚህ ወር ጀምሮ አቶ ረዳና ልጆቻቸው መኸር ሰብስባውን የተያያዙት ሲሆን ባቄላ፣ ዳጉሣ፣ ኑግና ተልባ በመድረሳቸው ሥራው እየከበደና እየተጠናከረ መጥቷል:: በሕዳር ወር አጠቃላይ የሆነ የሃይማኖት ክብረ-በዓል ባይኖርም አንዳንድ ኅብረተሰቦች ባህላዊ ጀግኖቻቸውን ለማስታወስ አነስተኛ ክብረ-በዓል ይኖራቸዋል::

ተከታዩ የታህሳስ ወር ፀሐያማና ደረቅ ነው:: አቶ ረዳና ቤተሰቦቻቸው የደረሰውን እህል በመሰብሰብ ከፍተኛ ርብርቦሽ የሚያደርጉበት ወቅት ነው:: ለአጨዳ ከደረሱት ሰብሎች መካከል ጤፍ፣ ስንዴና በዚህ ዓመት ሁለተኛ ሰብል ሆኖ የደረሰው ባለሁለት ረድፉ ገብስ (በልጋ) የመሳሰሉት ናቸው:: አቶ ረዳ አስቀድመው የመጀመሪያውን የ«በልጋ» ምርት በመስከረም ወር ወቅተው ወደቤታቸው ያስገቡ ቢሆንም መሬቱ በቂ እርጥበት በማግኘቱ ሁለተኛውን የገብስ ምርት ለማግኘት ችለዋል:: አንዳንድ ዘመን የዝናቡ ወቅት በመኸር ወራት ከቀጠለ ለሦስተኛው ጊዜ ይህንኑ ሰብል ማምረት እንደሚችሉ ነው የሚታወቀው:: በዚህ ወር አቶ ረዳና ቤተሰቦቻቸው አዝመራቸውን እየሰበሰቡ ወደ ቤታቸው ወስደው ጐተራዎቻቸውን ስለሞሉ የመንፈስ እርካታና ደስታ እንደሚያገኙ አይጠሬጠርም:: ጥረት-ግረታቸው ከተገቢው ሥርዓተ-ጸሎት ጋር ተጋግዘው እንደገና የተትረፈረፈ ምርት እንዲያገኙ ረድቷቸዋል::

በዚህ ወቅት በተለያዩ ማኅበረሰቦች በክብርዋ ስም በሚ ጠሩ ድግናዎች የክብረ-በዓል ሥነሥርዓቶች ይካሄዳሉ:: በተመሳሳይ ጊዜያት ዋላጅ በሚገኘው የክብርዋ ወንድም በካዲስቲ ስም በሚጠራው ድግና እና ከስጊ በሚገኘው የክብርዋና የካዲስቲ አባት የአይደርኪ ጓደኛ በሆነው በጀገሪሆ ስም የተሰየመው ድግና የክብረ-በዓል ሥነሥርዓቶች ይደረጋሉ::

በምዝግና ለጋስነት በተገኘው ስጦታ የመደሰቻ ወቅት:: በአምስተኛው ወር ጥር ላይ የአየሩ ጠባይ ፀሐያማ መሆኑን በመቀጠል መሬቱ በጣም እየደረቀ ሲሄድ ወንዞችም በጣም ይጉድላሉ:: የበጋው ሙቀት እንደቀጠለም ጋራዎች ወደ ወርቃማ ብጫማነት መለወጥ ይጀምራሉ:: እነ አቶ ረዳ ጤፍ አጨዳውን ተያይዘውታል፡ ሽምብራውም ስለደረሰ ከደረቀው መሬት ላይ እየነቀሉ በመሰብሰብ ላይ ናቸው:: እህል እየወቁ ማስገባቱም ከፍተኛውን የሥራ ድርሻ በመያዝ ቀጥሏል:: በዚህ ወቅት ጥጋብ ነው፡ የመዝናኛ ጊዜ ስላለ ከአካባቢው ኅብረተሰብ ውጭ ያሉትን ዘመድ አዝማድ ለመጠየቅ አጋጣሚው አሁን ነው:: የመኖርና የኑሮን ትርጉም ቅማንቶች የሚያጣጥሙት በአሁኑ ጊዜ ነው:: በአንድ እጃቸው አንድ ዋንጫ ጠላ፣ በሌላው ደግሞ ወፍራም የሆነ የዳቦ ቁራሽ ይዘው አቶ ረዳ ስለተሰበሰበው ሀብታቸውና ስለመጭው ወራት በሃሣባቸው ያብሰለስላሉ::

ስድስተኛው ወር የካቲት ሲመጣ በአብዛኛው ሞቃታማና ፀሐያማ ይሆናል:: አንዳንድ ዘመንም ጨርሶ ድርቅ የሚሆንበት ወቅት አለ፡ ወይም ደመናማ በመሆን ዝናብ ያንጠባጥባል፡ ለአንድና ለሁለት ቀንም ከባድ ዝናብ ሊጥል ይችላል:: ይህም ለሁለት ወራት ያህል ሊቀጥል የሚችለውን የትንሿን ክረምት (በልግ) ዝናብ ወቅት መምጣት የሚያበስር ነው:: በየካቲት ወር የሥራው ሸክም እየተቃለለ ስለሄደ አቶ ረዳና ቤተሰቦቻቸው ስለምርት ያላቸውን ትኩረት በመቀነስ የበለጠ ጊዜያቸውን ለፈንጠዝያ ያውሉታል:: የመጨረሻው ምርት የሆነው ሽንብራ ይነቀላል፣ ጤፍም እየተወቃ ወደ ቤት እየገባ ነው:: በመጠኑ ትንሽ እርሻ ይታረሳል፡ እንዲሁም አዳዲስ ቤቶችን መሥራትና አሮጌ ቤቶችን መጠገንም አለ:: ከምርት ስብሰበው በኋላ የመዝናኛ ጊዜና ብልፅግናውም ስላለ የተለያዩ በዓላትን ማክበር ያስችላቸዋል:: የተዝካር ድግስና ሠርግ በአብዛኛው በዚህ ወር ነው የሚደረገው:: አቶ ረዳና ባለቤታቸው ወይዘሮ አዳነች ትንሽ

ልጃቸውን መልኬን ለመዳር ሽር ጉድ እያሉ ነው። ስለሠርጉ ዝግጅት ዘወትር ይወያያሉ። መልኬም የሚዳር መሆኑን በመገንዘብ እንደ ድሮው «ታናሹ ወንድም» መባሉን እየረሳ የጉረመስ መሆኑን እየተገነዘበ ነው።



ገበሬዎች በአዝማሪ ዜማ እየተበረታቱ የገብስ አጨዳ በኅብረት ሲያካሂዱ

በየካቲት ወር ክርስቲያን የሆኑ ኢትዮጵያውያን በሙሉ አርባ ፆምን ለመቀበል መዘጋጀት ስላለባቸው ለየት ባለ መልኩ ብዙ ሥጋ መብላት ያዘወትራሉ፡፡ ሥጋም ሆነ ወተት ወይም እንቁላል በዚህ የሃምሣ አምስት የፆም ቀናት ውስጥ አይበላም፡ ከዚህም በስተቀር ከቅዳሜና ከእሑድ በስተቀር በሌሎች ቀናት እስከ ቀትር ድረስ እህል ንክች ማድረግ የለም፡፡ አረማዊ-አሬታዊ ቅማንቶች አርባ ፆምን አይፆሙም፡፡ ብዙዎቹ ክርስቲያን ቅማንቶችም ቢሆኑ በአክራሪ መልክ አይፈጽሙትም፡ ቢሆንም የዚህ የፆም ጊዜ ከቅማንቱ የክብረ በዓል ሥነሥርዓቶች ጋር የሚገጣጠሙበት ሁኔታ ስላለ ፆሙ በእነሱም ላይ ተፅዕኖ አለው፡፡ በጭልጋ አካባቢ ከአርባ ፆም መግቢያ ጀምሮ እስከ ደብረዘይት ድረስ በቅዱስ ድግናዎች የሚደረግ ሥነሥርዓት ባይኖርም የደብረዘይት ዕለት ቅማንቶች ሁለት የበልግ ወትት የልምላሜ ሥርዓተ-ቅዳሴዎች ያካሂዳሉ፡፡ ይኸውም አንዱ በከርከር ሌላው ደግሞ በጭልጋ የሚደረጉ ናቸው፡፡

የመጨረሻው የፍርድ ቀን (ምፅአተ-ዓለም) እና የበልግ ወትት ሥርዓተ-ቅዳሴ፡፡ የዓመቱ ሰባተኛ ወር በሆነው በመጋቢት የአየሩ ጠባይ ለስለስ ባለ መልኩ ቢቀጥልም ፀሐይ አልፎ አልፎ በደመና እየተሸፈነች ለአጭር ጊዜ ጠንካራ ዝናብ ሊጥል ይችላል፡፡ አቶ ረዳና ጐረቤቶቻቸው ትኩረታቸው እየተቃረበ በመምጣት ላይ ስላሉት ክብረ-በዓላት ቢሆንም በዚህ ወር ቤት መሥራትና መጠገን፣ እንዲሁም እርሻ ማረስ አለባቸው፡፡

ምንም እንኳን ሁሉም የከርከር ቅማንቶች ክርስቲያን ቢሆኑም በመጋቢት ወር አይነር የተባለው የቅማንቱ ዋና የባህል ጀግና ሚስት በሆነችው በእንተላ ስም በተሰየመው ድግና አነስተኛ የሆነ ዓመታዊ የልምላሜ ክብረ-በዓል ያከብራሉ፡፡ ቅማንቶች እንደሚሉት ለእንተላ ከተሳሉ መካን ሴቶች ይፀንሳሉ፣ የታመሙ ሰዎች ይድናሉ፤ እንዲሁም ድሆች ይበለጽጋሉ፡፡ በጥንቱ ዘመን እንተላ በሴት የልምላሜ ተመላኪነት የተመደበች መሆኗን እንገነዘባለን፡፡ በከርከር አካባቢ የሚገኙ ቅማንቶች ከእንተላ ክብረ-በዓል ጋር ተያይዞ ቀደም ብሎ ከዓርብ ሌሊት ጀምሮ ከዚህ በበለጠ ሁኔታ የሚከበረውና የሚታሰበው ምዝግና (እግዚአብሔር) ለመጨረሻ ፍርድ («ሻማሁላ» ወይም ለምፅዓተ-ዓለም) ወደዚች ምድር ይመጣል ተብሎ ስለሚገመት እሱን ለመቀበል የሚደረገው

የዝግጅት ሥነሥርዓት ነው:: ቀደም ብሎ እንደተገለፀው ይህ ሁኔታ ይከሰታል ተብሎ የሚታመነው የእንተላ ክብረ በዓል በሚከበርበት የደብረ ዘይት ዕለት ነው::

በጭልጋ የሚኖሩ ቅማንቶች የምዕዓተ-ዓለም (ሻምሁላ) በዓልን አስበው አያከብሩም:: ሆኖም በከርከር የእንተላ ክብረ-በዓል እሁድ እለት ከመካሄዱ በፊት ዓርብ ዕለት ጸሎት በማድረስ «መቁንን» እየተባለ የሚጠራውን የሸንብራ ቂጣ ይበላሉ:: በጭልጋ የሚገኙ ቅማንቶች በምን ምክንያት ይህ ሥርዓተ-ጸሎት እንደሚያካሂዱ ከጊዜ ወዲህ ቢረሱትም፣ የሽምብራ ቂጣ የሚመገቡት ምክንያት ለምዕዓተ-ዓለም (ሻማሁላ) ቅድመ ዝግጅት የፆም ሥነሥርዓት ሳይሆን አይቀርም የሚል አስተያየት አለ::

በተጨማሪም ይህን ቂጣ በመመገብ የሚደረገው ሥርዓተ-ጸሎት የኦሪት ሃይማኖት ተፅእኖ ያለበት መሆኑን የሚያስረዳ ከመሆኑም በላይ ፈላሻ አገዎች በአሁኑ ጊዜ ከሚያከብሩት ኦሪታዊ ከሆነው የፋሲካ በዓል ጋርም ተመሳሳይነት ስለአለው ተአማኒነቱን ያጠናክራል:: «የቂጣ በዓል» ተብሎ የሚታወቅበት ምክንያት ፈላሻዎች በዚሁ ዕለት ከዱቄት፣ ውሃና ጨው ጋር ተደባልቆ የተጋገረ ቂጣ ብቻ ስለሚበሉ ነው::

በምዕራባዊ የቅማንት አካባቢ ያሉት ኅብረተሰብ የሚያከብሩት ዋና ክብረ በዓላቸው የሽምብራ ቂጣው በዓል እንደተከበረ በሚቀጥለው ዕሑድ ቀን የከርከር ቅማንቶች በአነስተኛ ሁኔታ ከሚያከብሩት የእንተላ የልምላሜ በዓል ቀን ጋር ይገጣጠማል:: በዚሁ ቀን የጭልጋው ወምበር በሚቀጥለው ወራት የእርሻዎችና የሰዎች ልምላሜ እንዲታደስ የበልጉን ወቅት ዓመታዊ ሥርዓተ-ቅዳሴ ያካሂዳል:: ይህ ሥነሥርዓት ምናልባት የኦሪትና የክርስቲያን ሃይማኖቶች ወደ ቅማንት ከመድረሳቸው በፊት የነበረ ጥንታዊ ሥርዓት ሳይሆን አይቀርም:: ጥንታዊ ስሙ የተረሳ በመሆኑ በምዕራብ ቅማንት አካባቢ የሚኖሩ ቅማንቶች ከክርስቲያኑ የደብረ ዘይት በዓል ጋር አንድ ቀን የሚውል ስለሆነ የደብረ ዘይት በዓል ብለው ይጠሩታል::

ምንም እንኳን በቅማንት ምሥራቃዊ ክፍል በአሁኑ ጊዜ ስለልምላሜ የሚደረገውን ዋና ዓመት በዓል የማያከብሩ ቢሆንም ከአሥር ዓመታት በፊት በግንቦት ወር መባቻ «ፋዛን» ተብሎ

የሚታወቀውን በዓል ያከብሩ ነበር፡፡ ከፍ ብሎ እንደተገለፀው አንስተኛ የሆነው የእንተላ የልምላሜ ክብረ-በዓል አከባበር ትውፊት እንደነበረ እንገነዘባለን፡፡

የወምበሩ መንደር በሚገኝበት በምዕራባዊ ቅማንት ጭልጋ ውስጥ ጃልሽብ በተባለ ቦታ እ.ኤ.አ. መጋቢት 28 ቀን 1965 ዓ.ም. እሑድ ቀን (መጋቢት 19 ቀን 1957 እ.ኢ.አ.) ዓመታዊ የልምላሜ ክብረ-በዓል በተከበረበት ወቅት የሥነ-ሥርዓቱ ተካፋይ ነበርኩ፡፡ የዕረፍት ቀን በሆነው በዚሁ ዕለት በጥዋቱ የቅማንት ሴቶች የጸሎት ቤቱን አፀዱት፡፡ ለዕለቱ ድግስ የሚሆነውን ምግብ የሚያዘጋጁት ዕድሜያቸው የገፋ፣ ያረጡና በ«ካሣ» ሥነሥርዓት ያለፉ ሴቶች ነበሩ፡፡ ዝግጅቱ ከተጠናቀቀ በኋላ በግምት በ3 ሰዓት አካባቢ ሁለት ቀሳውስት ጸፕ ብሎ በተቀመጠው ወምበር ፊት ለአንድ ሰዓት ያህል ቆመው ሲጸልዩና ሲቀድሱ ቆዩ፡፡ ወጣ ብሎም በምድረ ግቢው በርካታ ሕዝብ ተሰብስቦ ለአንድ ሰዓት የሚደረገውን ጸሎትና ቅዳሴ ይከታተል ነበር፡፡ ቅዳሴው በሚካሄድበት ወቅት አልፎ አልፎ ሕዝቡ ፊቱን ወደ ምሥራቅ በማዞር በግንባር በመደፋት ምርት የምትለግሳቸውን መሬት ይስማል፡፡ በሌላ ጊዜ ደግሞ ምግብ የሚቀበሉ በማስመሰል ሲንበረከኩ መዳፋቸውን በአንድ ጊዜ ሁሉም ወደሰማይ ይዘረጋሉ፡፡

ሥርዓተ-ጸሎቱ ካለቀ በኋላ ወምበሩና ቀሳውስቱ በጃልሽብ ወደሚገኘው መስዋዕት ማቅረቢያ በእግራቸው ሄዱ፡፡ እንደተለመደው መስዋዕት የሚደረጉ በጐች ባለመኖራቸው የወምበሩ እናት ስድስት ነጫጭ ዶሮዎች እንዲያመጡ በአጠገባቸው ለሚገኙት ልጆች ትዕዛዝ ሰጡ፡፡ እንዳመጡም የዶሮዎችን እግር ዝቅተኛው ቄስ እየያዘለት ከፍተኛው ቄስ በሙሉ ባረካቸው፡፡ ከዚያም ከፍተኛውና ዝቅተኛው ቄሶች በትልቅ ሽክና ጠላ ቀድተው ከፊሉን መሬት ካለው የዶሮ ደም ላይ ሲያፈሱት ቀሪውን ከእጃቸው ላይ በማድረግ ጠጡት፡፡ በመጨረሻም ለቀሳውስቱ በተለየ ድስት እንዲሠራላቸው ከእያንዳንዱ ዶሮ የቀኝ ጭን ከፍተኛው ቄስ በመገንጠል ወስዶ ለሚሠሩት ሰጠ፡፡ ቅማንቶች በበዓላት ምክንያት በሚደረጉ የጸሎትና የመስዋዕት ሥነሥርዓት በሚጠናቀቅበት ጊዜ ያም እንዲፈቱ ሁሉም ትንሽ ትንሽ ምግብ ይሰጣቸዋል፡፡ በዚህም መሠረት ምግቡን ከቀመሱ በኋላ በመጠኑ ሲጠጣና ሲበላ እስከ ዘጠኝ ሰዓት ቆይቶ ዋናው

ግብዣ ቀጠለ። ከዚያም ዶሮ ወጥ ሳይቀር የተለያየ ወጥና እንጀራ ቀርቦ በጠቅላላው የተንበሸበሸ ግብዣ ተደረገ።

ከግብዣው በኋላ የመጨረሻና ዋናው ሥነሥርዓት መካሄድ ነበረበት። የተለያዩ የእህል ዘሮች በሰፌድ ላይ ተደርገው ወደ አንድ የእርሻ ቦታ ከተወሰዱ በኋላ ሕዝቡ ተሰብስቦ ፊቱን ወደ ምሥራቅ በማዞር መጸለይና መሬቱን መሳም ቀጠለ። ቄሶችም በዘሮች ላይ ጸሎት ካደረጉና ከባረኩ በኋላ ሁለት የእርሻ በሬዎች ተጠምደው ወምበሩ በማሳው ላይ አንድ ሾር ካረሱ በኋላ ከቄሶቹ ጋር ሆነው በተባረከው ሾር ላይ ዘሮችን በመዝራት የተባረከውን ጠላ (መስኪ) አፈሰሱበት። ሳይዘራ የቀረውንም የተባረከ ዘር ተሰብስቦ የነበረው ሕዝብ ተቃመሰው። ይህ ሥርዓተ ጸሎት ጤናና ልምላሜውን እንደሚሰጣቸው ይተማመኑበታል። ስለዚህም ነበር ይህን የተባረከ ዘር የቀመሱ መካን ሴቶች በመፀነሣቸው ወምበሩ ለዋሉላቸው የጸሎት ውለታ በዚሁ ሥነሥርዓት ልዩ ስጦታ ያበረከቱት።

የሚቀጥለው ቀን ደግሞ የዕረፍት ቀን ሆነ። በዚሁ ዕለት ወምበሩና ቀሳውስቱ በአጠገባቸው ወደሚገኝ ቅዱስ ድግና በመሄድ መጭው ጊዜ የተሣካ የእርሻ ወቅት እንዲሆንላቸው ለማረጋገጥ ሥርዓተ-ጸሎት ያደርሳሉ። ከእንግዲህ የልምላሜው ሥርዓተ-ጸሎት የተጠናቀቀ በመሆኑ ዘር መዝራት በቅርቡ ይጀመራል። የተደረገው ሥርዓተ-ጸሎት፣ የፈሰሰው የመስዋዕት ደም፣ የተባረከው ሾር፣ የተዘራው ዘርና እዚያው ላይ የተረጨው የተቀደሰ ጠላ ለሚቀጥለው ወቅት መሬት ልምላሜዋን እንደምትለግሳቸው በመተማመን ትግንቶች «የሚገኘው ምርት እርግጠኛ ከፍተኛ ይሆናል!» በማለት መፈክራቸውን አስምተው የልምላሜው ክብረ-በዓል ሥነሥርዓት ፍጻሜ ሆነ።

የዘር ወቅት። የመስክ ጥናቱን በማካሂድበት በ8ኛው ወር ሚያዚያ ላይ አልፎ አልፎ የበልግ ዝናብ በመጣሉ በከርከር የሚገኙ ጋራዎች በመጠኑም ቢሆን ወደ አረንጓዴነት ተለውጠ ዋል። እርሻ፣ ቤት የመሥራቱና የመጠገኑ ተግባር በአቶ ረዳና በጉረቤቶቻቸው እየተጣደፈ ነው። የአየሩ ጠባይ በአጠቃላይ ሞቃታማና ፀሐያማ ነው። ያን ጊዜ ነበር እርፍ ጨብጬ እርሻ ለማረስ የሞከርኩት። ነገር ግን ወዲያውኑ ከኋላ ደርሺ እርፉን ከመያዜ በሬዎቹ ቀንበሩን ከላያቸው በኃይል በማስወገድ

ዓይናቸውን በመጉልጉል ከተመለከቱኝ በኋላ ደንብረው ወደ ቁልቁለቱ ነጉዱ። ትሁቱ የትግንት ገበሬ ዘወትር በሳሙና በመታጠቢ ያልተለመደ ወዝ ሽቶአቸው ነው የደነበሩት ከማለት ይልቅ፣ በሬዎቹን «ስላስደነገጥኳቸው ነው» በማለት ነበር ነገሩን ያለፈው። በሬዎችን አባርሮ ለመያዝ እርዳታ እንዳደርግ ብጠይቅም «ለዛሬ የሠራኸው ሥራ በቂ ነው ተወው» ተብዬ ተሰናበትኩ።

እንደተለመደው በሚያዚያ ወር ወንዶቹ ያለማቋረጥ ከጥዋት እስከማታ በሥራ ተጠምደው በመዋል የእርሻ መሬቶችን ለዘር ያለሰልሳሉ። ቢሆንም አሁንም ትንሽ ጊዜ አይጠፋም። በመሠረቱ ዘር መዝራት የሚጀመረው በሚያዚያ ወይም በሚቀጥለው ወር ቢሆንም ወሳኙ ጉዳይ ግን እህል ለማብቀል የሚያስችል በቂ ዝናብ መኖሩ ነው። ምንም እንኳን ለልምላሜ ተብለው ባለፉት ወራት የተደረጉት ሥነሥርዓቶች የእጺሶችን ሰብሎች ምርታማነት አስተማማኝ እንደሚያደ ርጓቸው ቢኸዘቡም ማንኛውም ትክክለኛ አእምሮ ያለው ቅማንት መሬቱ በቂ እርጥበት ካላገኘ ዘሩን እንዲሁ አይበትንም።

ዘጠነኛው ወር ግንቦት ሲደርስ የበልጉ ዝናብ በጣም እየቀነሰ ስለሄደ አረንጓዴ የነበሩትም የከርከር ጋራዎች ሣሩ መድረቅ ስለጀመረ ወደ ብጫነት መለወጥ ጀምረዋል። በተለይ በጭልጋ በዚህ ዓመት ዝናቡ በበልግ ወራት ባለመጣሉ ካለፈው ጊዜ በጣም ያነሰና በግንቦት ወርም ጨርሶ ባለመጣሉ ጋራዎች በሙሉ በእሳት የተለበለቡ ይመስላሉ። በሁለቱም አካባቢዎች የአየሩ ጠባይ ሞቃታማና የሚያቃጥል ነው። ቤት መሥራትና እርሻውም መታረስ ቀጥሏል። በግንቦት ወር ዋናው ሥራ ዘር መዝራት ቢሆንም በዚያ ዘመን መሬቱ በጣም ስለደረቀ የዘሩን ወቅት ማዘግየት ግድ ሆኖአል። በጭልጋ አካባቢ በግንቦት ወር መጨረሻ ትንሽ ማሽላ፣ ኑግና ተልባ ይዘራሉ፣ በከርከር ደግሞ ባለሁለት ረድፍ ገብስ (በልጋ) የሚዘራበት ወቅት ነበር፤ ሆኖም ድርቅ በመሆኑ አልተቻለም።

ቀደም ብሎ በዝርዝር እንደታየው የግንቦት መባቻ «ፋዛን» የተባለው የልምላሜ ክብረ በዓል በከርከር የሚከበርበት ቀን ነው። በአሁኑ ጊዜ እየተረሳ ለምልክት ያህል አንዳንድ ሰዎች በቤታቸው ውስጥ ጸሎት ከማድረግና ምግብ ከማብላት በስተቀር ሌላ ጉልቶ

የሚታይ ነገር የለም። ይህን ሥነሥርዓት ክርስቲያን አማራዎች በቅድስት ማርያም ልደት ምክንያት ልዩ ምግብ በማዘጋጀት ቤተሰብና ጉረቤት ተሰብስቦ ከሚያከብሩት በዓል ጋር ይገጣጠማል።



ወምበሩ በፀደይ ልምላሜ ሥርዓተ-ጸሎት የተባረከውን ሾር ሲያርሱ።

በግንቦት ወር ዝናብ ሲጠፋ በጭልጋ የሚገኙትን አረማዊ-አሪታዊና ክርስቲያን ቅማንቶችን ጭምር የሚያስጨንቅ ችግር ነው:: በመሆኑም በጭልጋ የሚገኙ ኅብረተሰቦች የቅማንት ቀሳውስት ዝናቡ እንዲስተካከል የጸሎት ሥነሥርዓት እንዲደረግ ስለተማፀኗቸው ወምበሩ የመረቻቸው ሁለት ሥነሥርዓቶች እ.ኤ.አ. ሚያዚያ 27 ቀን 1965 ዓ.ም. እና እ.ኤ.አ. ግንቦት 11 ቀን 1965 ዓ.ም. በተከታታይ ተካሂደው ነበር:: ለመስዋዕት የሚሆኑትን በጐች በአካባቢው የሚገኙ ገበሬዎች አዋጥተው አዘጋጅተው በልምላሜ በዓል እንደሚደረገው ሁሉ ጸሎትና መስዋዕት የማቅረቡ ሥነሥርዓት አዳሪ ፈርዳዳ (የእግዚአብሔር ፈረስ) በተባለው ቦታ እንዲካሄድ ተደርጓል:: በዚህ ሥነሥርዓት ላይ በጣም ጥቂት ሰዎች ስለነበሩ የታረዱትን በጐች የሃይማኖት አባቶች ከእኩለ ቀን በኋላ እንዲበሉዋቸው ተውላቸው:: ሌሎች ተመሳሳይ ሥነሥርዓቶች በዚሁ ጊዜ በምዕራብ ጭልጋ የቆሌዎች መኖሪያ ናቸው በተባሉ ቦታዎችም ተካሂደዋል::

ይህም ሁሉ ሥነሥርዓት ተካሂዶ ዋናው ክረምት መግባት ከነበረበት ጊዜ ዘግይቶ ነበር:: ዝናቡ እስከ ሰኔ አጋማሽ ድረስ ሳይመጣ ድርቅ ሆኖ ቆየ:: ሰኔ አጋማሽ ላይ ዝናቡ በመዝነቡ አቶ ረዳና የአካባቢው ኅብረተሰብ የዘር ወቅት መሆኑን ተገንዝበው በዚሁ ላይ መረባረብ ጀመሩ:: እርሻና ቤት ጥገናውም ወሩን በሙሉ ጐን ለጐን የሚከናወኑ ተግባሮች በመሆናቸው ፋታ አልነበራቸውም::

በሰኔ ወር ውስጥ ወምበሩ ጭልጋ ውስጥ እንዘይመርቁ በተባለ በተባረከ የፀበል ቦታ የጸሎት ሥነሥርዓት መርተው ነበር:: ይህ ተዓምረኛ ፀበል የታመሙትን እንደሚያድንና መካኖችንም እንዲወልዱ የሚያደርግ መሆኑ ይነገራል:: የጸሎቱና የፀበል መጠ ጣቱ ሥነሥርዓት የሚካሄደው ከቅዳሜ እስከ ዕሑድ ሌሊት ድረስ ስለነበር ወደ ጠበሉ የመጡት እንደ አቶ ረዳና ሌሎች መሰል የኅብረተሰቡ አባል የሆኑ ግለሰቦች ጸሎታቸውን በማድረስ ለሁለት ሌሊት ምግብ መጋበዝ ነበረባቸው:: ጋርጊ በመባል በታወቀው መልአክ ስም በዓመት ሦስት ጊዜ የሚከበረው በዓል የመጀመሪያው የሚውለው ሰኔ ወር ውስጥ ነው:: እነዚህ ክብረ በዓላት በአሥራ አምስት ቀናት ተራርቀው ነው የሚከበሩት::

እሥራ እንደኛው ወር ሐምሌ በየቀኑ ዶፍ ዝናብ ይወርዳል:: ቀስ በቀስም እያሰለሰ ከባድ ዝናብ ሲጥል ቆይቶ በመጨረሻዎቹ ሁለት ሳምንታት ደግሞ ዝናቡ እየቀነሰ ይመጣል:: አቶ ረዳና ሦስቱ ልጆቻቸው እያረሱ ዘር በመዝራትና ባለፈው ዓመት አጥረውት የነበረው አጥር በበጋው ወራት ስለተነካ በትሎ በማደግ ላይ ያለውን ሰብል ከብት እንዳይበላው በሌላ ለመተካት በመጣደፍ ላይ ናቸው:: በሐምሌ ወር በቂ ውሃ በመኖሩ የባሕር ዛፍ ችግኞችንም ይተክላሉ:: አቶ ረዳ በቤታቸው አካባቢ ትንሽ ዛፎች ቢኖሩዋቸውም በተጨማሪ ለልጅ ልጆቻቸው መትከል ነበረባቸው:: ጐመን የወቅቱ መጀመሪያ ደራሽ የሚበላ የጓሮ አታክልት በመሆኑ (ብዙ ባይወዱትም) የአቶ ረዳ ቤተሰብ እየቀነጠሱ ከትፊው በመቀቀል ይመገቡታል:: አንድ ቀን አቶ ረዳ ከኔ ጋር እንዲበሉ ጋብዣቸው ሥጋ፣ ድንችና ጐመን ቀርቦ እየበላን እያለ «ሥጋ እያለ ለምን ጐመን ይበላል?» በማለት ስለጐመን ያላቸውን ዝቅተኛ ግመት የገለጹልኝን አልረሳውም::

«የክብረ-በዓል መዝጊያ» (በዓል ዓለሜ) የጥንቱ የባህል ትውፊት ሲሆን ብዙ ጊዜ በከርከር በአንዳንድ የተለያዩ ቡድኖች ታስቦ ይውላል:: ይህን የተረሳ ሥነሥርዓት አሥርም ሆኑ ቁጥራቸው ከዚያ በላይ የሆነ ወንዶችና ሴቶች በአንድ ላይ ተሰብስበው በግ አርደው በመብላትና ቡና አፍልተው በመጠጣት ያከብሩታል:: ጸሎት ከማድረስ በስተቀር የሥጋታቸው የሚያረጋጋ የተለየ የቅዳሴ ሥነሥርዓት አይደረግም:: በአሁኑ ጊዜ የጥንቱ ሥርዓት አባል የሆኑ ቄሶች በከርከር ስለሌሉ እስከ ቅርብ ጊዜ ድረስ ሲደረግ እንደነበረው የክብረ-በዓል መዝጊያው በትልቅ ስብሰባ አይከበርም:: በዚሁ ወቅት እንዲሁ በጣም ዝናብ ስለሚበዛ መንቀሳቀስ ከማይቻልበት ጊዜ ጋርም ይገጣጠማል::

እሥራ ሁለተኛው ወር ነሐሴ ከፍተኛው ዝናብ የሚዘንብበት ጊዜ ቢሆንም፣ ባለፈው ዓመት በነበርኩበት ጊዜ ይጥል ከነበረው ዝናብ በጣም ያነሰ ነበር:: ዝናቡ በሚበዛበትና ደመናማ በሆነበት ጊዜ እንኳን በከርከርም ሆነ በጭልጋ የሙቀቱ ልክ ከ60 ዲግሪ ፋረንሐይት ወርዶ አያውቅም:: ብዙ ውሃ የበዛበት መሬት የሚፈልገው ጤፍ የሚዘራው በዚህ ወር ነው:: ጥራጥሬና የቅባት እህሎች በማደግ ላይ ሲሆኑ ደብዛዛ አረንጓዴ መልክ ያለው ገብስ ከሁለት እስከ ሦስት ጫማ ቁመት አድጐ ነፋስ ሲያወዛውዘው ልክ እንደማዕበል የሚተም ይመስላል::

ተልባና ዳጉሣ ትንሽ ከፍ ብለዋል፡ እንዲሁም የቅባት እህል የሆነው ኑግ አረንጓዴ አገዳው እንደ ጫካ ያህል አድጓል፡፡ ድንች ደርሶ በመሰብሰብ ላይ ሲሆን ጐመኑም ደርሶ እየከረደደ ነው፡፡ በዚህ ወቅት የቅማንት ቄሶችና አባውንቶች ሙሉውን የነሐሴን ወር ይፆማሉ፡፡

በዓመት አምስት ቀንና በአራተኛው ዓመት ደግሞ ስድስት ቀን ያለው የኢትዮጵያ 13ኛ ወር የሆነው ጳጉሜን ከነሐሴ ወር ይቀጥላል፡፡ በዚህ ዘመን ዓመቱ በተለየ መልክ ድርቅ ስለነበር ጳጉሜን ውስጥ አንድ ቀን ብቻ ነበር የዘነበው፡፡ እስካሁን ያልተዘራ እህል ቢኖር ሽምብራ ብቻ ነው፡፡ ሌሎች ሰብሎች በማደግ ላይ ሲገኙ በሊጋ የሚባለው ገብስ ግን ወደ ደብዛዛ ቢጫነት ተለውጦ ለአጨዳ ደርሷል፡፡ በቅድመ-መኸር በድሃ ገበሬዎች ከሚከሰተው ረሃብ ከድንችና ከጐመን ቀጥሎ ከችጋር የሚያተርፋቸው ባለ ሁለት ረድፉ ገብስ (በሊጋ) ነው፡፡ ይህ የገብስ ዓይነት ሌላው ቀርቶ እሸቱ እንኳን ሊበላ የሚችል ነው፡፡ አንዳንድ ዘመናት የመጨረሻዎቹ አንድ ወይም ሁለት ወራት የዘመኑ ምርት ዝቅ ያለ ከሆነ አንድ ሰው ለችግሩ መሸጋገሪያ እንዲሆንለት አንድ ከብት ሸጦ እህል መሸመት ይገደዳል፡ ሌላው አማራጭ ደግሞ ትርፍ ካለው ዘመድ ወይም ጓደኛ መበደር ይሆናል፡፡ ሆኖም አቶ ረዳ ለምግብና ለዘር የሚሆን በቂ እህል ስለነበራቸው አልተቸገሩም፡፡ በዚህ ወቅት ብዙ ገበሬዎች በየጊዜው ጐተራቸው እየተራቆተ ጐመን ብቻ እየበሉ ያሳለፉትን ጊዜያት ያነሣሉ፡፡ የአቶ ረዳ አባት አቶ አየነው ልጅ በነበሩበት ጊዜ ተከስቶ ብዙ ሕዝብ የጨረሰውን የረሃብ ዘመን ሲያስታውሱ ግን በጣም ይሰቀጥጣቸዋል፡፡ ቢሆንም በአስቸጋሪ ሁኔታ ከመሞት መሰንበት የሚመርጥ መሆኑን ቅማንቶች በተረት ሲገልፁት «ከሞተ ንጉሰ ይሻላል በቁም ያለ ድሃ ገበሬ» ይላሉ፡፡

አዲሱ ዓመትና አዝመራ፡፡ መስከረም ለክርስቲያኖች የዓመቱ የመጀመሪያ ወር ሲሆን፡፡ ለቅማንቶች ደግሞ የሃይማኖት እንቅስቃሴዎቻቸውን ዑደት የሚዘጉበት የመጨረሻው ወር ነው፡፡ የዚህ ወር የመጀመሪያው ቀን በሰሜናዊ ማዕከላዊ ኢትዮጵያ የከባዱ የክረምት ወቅት ማክተሙን የሚያበስር ነው፡፡ ነገር ግን በቅማንት አካባቢ የዝናብ ወራት የሚፈፀመው በሚቀጥለው የጥቅምት ወር ላይ በመሆኑ የቅማንት ክብረ-በዓሎች ዑደት ምናልባትም የተረሣው የመጀመሪያው የወራት መነሻ የሆነው ቀን

የመሬቱ እርጥበት ምጥጥ በሚልበት በጥቅምት ወር ሳይሆን አይቀርም። አዲሱ የዘመን መለወጫ (መስከረም አንድ) ዓመት በዓል ለቅማንቱ፣ ለአማራውና ለፈላሻው የዕረፍትና ልዩ ምግብ የሚበላበት ቀን ነው። አቶ ረዳና ቤተሰቦቻቸው ጥሩ ምግብ በመብላትና በመጠጣት ያለፈውን ዘመን የሚገመግሙበትና ወደፊቱ ደግሞ ምን ሊከተል ይችል ይሆን በማለት ሲያሰላስሉ የሚውሉበት ቀን ነው። በተጨማሪም አዲሱ ዘመን ዛሮች የሚሾሙበት ቀን ስለሆነ ለቃልቻው አዩ ሥራ የሚበዛበት ቀን ይሆናል። በዚሁ ቀን አዩ ሌሎች የዛር ችግሮችን ከመፍታቱ ሌላ አዲሱ ዓመት ምን ይዞ እንደሚመጣ የሚተነብይበት ዕለት ነው።

በጥቅምት ወር ዱባው ደርሶ እየተቆረጠ ነው፣ በሊጋው ደርቆ እየታጨደ ሲሆን ከስር ከስር ደግሞ በቂ ዝናብ በመገኘቱ ሁለተኛውን የበልጋ ምርት ለማግኘት ቃርሚያው እየታረሰ ዘር እየተዘራ ነው። በጥሩ ሁኔታ እርሻው ከተሳካ የተትረፈረፈ ምርት ስለሚኖርና ጉተራዎቻቸው ስለሚሞሉ በሚቀጥለው በቅድመ-መኸር ወቅት ሊከሰት ከሚችል ርሃብ ዋስትና ይኖራቸዋል። ውሃው እየጠነፈፈ መሬቱ እየደረቀ ሲሄድ የሰብሎችን የተለያየ ሕብረ-ቀለማት ማየት ዓይንን የሚማርኩ ከመሆኑም በላይ ጋራዎችም በተመሳሳይ ሁኔታ አሸብርቀው፣ ሜዳዎችና ሸንተረሮች በአደይ አበባ (እንቁጣጣሽ አበባ) ተንቆጥቆጠው፣ ማሳዎች አልፎ አልፎ በሰማያዊ የተልባ አበባ ተሸፍነውና እዚያና እዚህ በአበቡት የኩሸሽሌ ክፍት ቀይ አበባዎች ታጅበው አገሩ ደምቆ ሲታይ መላው የቅማንት አካባቢ ለፖስት ካርድ የተዘጋጀ ስዕል ይመስላል ማለት ማጋነን አይሆንም።

የጭልጋ ወምበር በቤታቸው ከሚያደርጉት የአንድ ቀን ጸሎትና ግብዣ በስተቀር በዚህ ወር በድግናዎች የሚደረጉ ክብረ-በዓላት የሉም። በሚቀጥለው የጥቅምት ወር በአቶ ረዳና ጉረቤቶቻቸው ዘንድ ሰብል ሰብሰባው በጣም ይፋፋማል፣ እንዲሁም ዓመታዊው የክብረ-በዓላት ዑደት እንደገና በአዲሱ ዘመን ይከፈታል። ወቅቱ እንደልብ መንቀሳቀስ የሚቻልበትና ጉተራዎችም ሞልተው ምግብ የሚትረፈረፍበት ጊዜ ነው። በዚህ ወቅት አቶ ረዳ፣ ልጆቻቸውና የልጅ ልጆቻቸው ልክ አባታቸው አቶ አየነው በዘመናቸው ያደርጉት እንደነበረው ሁሉ ለመጪው ዓመታዊ የኢኮኖሚያዊና መንፈሳዊ ዑደት ለሚያደርጉት ተሳትፎና ጥረት-ግረት እርቀው ማቀድ ይጀምራሉ።

# ምዕራፍ ዘጠኝ

## የምዝግና ሰዎች የሕይወት ዑደት

ቅማንቶች ከአንዱ የሰውነት ደረጃ ወደሌላው ሲሸጋገሩ የሚያደርጓቸው ሥነሥርዓቶች በሕይወታቸው ሂደት የሚያልፉባቸውን ልዩ ልዩ እርከኖች በግልጽ ያንፀባርቃሉ፡፡ አንድ ግለሰብ ከአንዱ ወደሌላው ሂደት ሲሸጋገር በመንፈሳዊ ሥነሥርዓቶች ይከበራሉ፡፡ አንድ ልጅ ተወልዶ የቅማንት ኅብረተሰብ አባል ሲሆን፣ ጉርምስ ሲያገባ፣ ሲሸመግል፣ ሞቶ ወደሌላው ዓለም ሲሸጋገር በየደረጃው የሚያካሂዷቸው ከሃይማኖት ጋር የተያያዙ ሥነሥርዓቶች አሏቸው፡፡ እንደነዚህ ዓይነት በምዝግና (በእግዚአብሔር) በጐ ፈቃድ የሚካሄድ ክብረ-በዓላት የቅማንት ኅብረተሰብን የሚያስተሳስሩና ቅማንቱ ከሌላው ኅብረተሰብ ጋር ሳይቀላቀል ልዩ የሆነውን ማኅበራዊ ሥርዓቱን ጠብቆ እንዲቆይ አድርጉታል፡፡ ከዚህ ቀጥሎ እያንዳንዱ ቅማንት በኅብረተሰቡ ውስጥ ባለው መዋቅርና በባህሉ ሥነምግባር መሠረት ሕይወቱን እንዴት እንደሚመራ እናያለን፡፡

## በሴት የወር አበባና በመጫትነት ወቅት የተከለከሉ ነገሮች

የሰውን የሕይወት ዑደት ለመዘርዘር ልጅ ከሚወለድበት ጊዜ ጀምሮ እስከ ዕለተ ሞቱ ድረስ ማየት የተለመደ ነው፡፡ ነገር ግን የቅማንቶችን የሕይወት ሂደትና ከዚህም ጋር ተያይዘው ያሉት ከአንዱ ወደ ሌላው ደረጃ የመሸጋገሩ ጉዳይ በዕለተ ሞት ብቻ ሳይገታ ከመቃብር በኋላም ሌሎች ሥነሥርዓቶች እንዳሉ ነው የምንረዳው፡፡ እንዲሁም በተመሳሳይ ሁኔታ ስለቅማንት የሕይወት ዑደት ስናጠና ልጅ ከሚወለድበት ጊዜ ጀምሮ ሳይሆን ከልደት በፊት ወደኋላ ሄደን አንዲት ለአቅመ ሄይዋን የደረሰች ሴትን ቅማንቶች በምን ዓይነት መልክ እንደሚመለከቷት መገንዘብ ይኖርብናል፡፡

የቅማንት ሴቶች የወር አበባቸው በሚመጣበት ጊዜና በሚወልዱበት ወቅት እንዳልፀዱ (እንደረከሱ) ስለሚታዩ ለአንድ ሳምንት ከኅብረተሰቡ ተገልለው ይሰነብታሉ፡፡ ይህ እምነትና ባህል በሌሎችም የአገው ሕዝቦችም ዘንድ ያለ ሲሆን ከሴቶች የሚፈሰው

ደም (መርገም) የሚያረክስና ጉድ ነው ተብሎ ይታሰባል። አንዲት ሴት በሥረዓተ-ቅዳሴ ቦታ ላይ መገኘት የምትችለውና ሙሉ በሙሉ ንፁሕ ናት የምትባለው ስታርጥ ብቻ ነው። ይህ የሰውነት ፍጥረታዊ ለውጥ እንደተከሰተ ወደ ማንኛውም ቅዱስ ቦታ መሄድና እንዲሁም ለሥርዓተ-ቅዳሴ የተዘጋጀውን ምግብና መጠጥ መጋበዝ ትችላለች።

የቅማንት ሴት የወር አበባዋ በሚመጣበት ወቅት በተለይ ለዚህ አገልግሎት ተብሎ በማንኛውም ቤተሰብ ቤት አጠገብ በተሠራ ጉጆ ውስጥ ትገለላለች። በምንም ምክንያት ጉጆዋን ለቃ መውጣት ስለማትችል ምግቧ በቤተሰቧ አማካይነት ይቀርብላታል። በምትነፃበት በሰባተኛው ቀን ጉጆውን ታፀዳለች፣ ሰውነቷን ታጥባና ልብሶቿን አጣጥባ ለብሳ ወደ ዕለታዊ ተግባሯ ትመለሳለች። በወር አበባ ጊዜ ይህ ለብቻ የመገለል ሁኔታ ትኩረቴን በጣም ሊስብ የቻለው አንድ ነገር ቢኖር በዚህ በተከለከለ ባህል (ታቡ) ምክንያት አንዲት ሴት ከእድሜዋ አንድ አራተኛ የሆነውን ወርቃማ የምርታማነት ጊዜ በእረፍት ላይ ማሳለፏ ነው። ስለዚህ ጉዳይ ከአንዳንድ የቅማንት ወንዶች ጋር ለውይይት አንስቼ ሳነጋግራቸው ያላቸው አቋም «ሴቶች ሥራ አይበዛባቸውም፣ አንዲት ሴት በወር አበባ ምክንያት ስትገለል የእሷ የሥራ ድርሻ በቤተሰቡ ባሉ ሌሎች ሴቶች ይሸፈናል» የሚል ነው። በአጠቃላይ በወንዶች እይታ የሴት ሥራ ሳይሠራ እንደማይቀርና ሴት ቁጭ ብላ ጠላ እየጠጣች ወሬ በማውራት እንደምትውል ነው ግምታቸው።

ከዚህ ጋር በተያያዘ መልኩ ሌላ የተከለከለ ባህል ቢኖር ሴቶች በሚወልዱበት ጊዜ የሚደረገው ማግለል ነው። አንዲት ሴት እርግዝ የመውለጃ ጊዜዋ ሲቃረብ ጊዜያዊ የሆነ የማግለያ ጉጆ ከዋናው ቤት አጠገብ ይሠራላታል። ሕፃኑ እንደተወለደ ልጇን ይዛ ወደ ጉጆው በመግባት ለሰባት ቀን ትቀመጣለች።

## የልጅ ልደት

አንዲት ሴት የመጀመሪያዋን ልጅ በእናቷ ወይም በአማቷ ቤት ትወልዳለች። ከዚያ በኋላ የሚመጡትን ልጆቿን ግን በራሷ ቤት ነው የምትወልደው። በቅማንት ቤተሰብ ልጅ በሚወለድበት ወቅት ከሚወስዱት እርምጃዎች ጋር ለመተዋወቅ ይረዳኝ ዘንድ ፀሐይ ከአማቶቿ በአቶ ረዳና በወይዘሮ አዳነች ቤት

የመጀመሪያዋን ልጅ በወለደችበት ወቅት የተወሰደውን እርምጃ እንመልከት።

አንድ ቀን ፀጥ ባለና አየሩ በመኸር ወቅት ሽታ በተሞላበት ሌሊት ፀሐይ ምጥ ተያዘች። ምጡ እየጠነከረ ስለመጣ ወይዘሮ አዳነች አብረው ከሚኖሩት ከጎረቤቶቻቸው በአዋላጅነት የታወቁትን እንዲረዱና ፀሐይን በምጡ ጊዜ እንዲያበረታቱ አስጠሯቸው። ምጡ ለፀሐይ በጣም አስቸጋሪ ቢሆን ኖሮ የአይደርኪ ሚስት የነበረችውን እንቶላ የተባለችውን የባህል ጀግና (ምልኪ) ለመለማመን ሴቶች ልዩ ጸሎት ማድረግ ይገደዱ ነበር። ሆኖም ፀሐይ የአሥራ ስድስት ዓመት ወጣትና ጠንካራ ሴት ስለነበረች ችግሩን በቀላሉ ተቋቁማ ወንድ ልጅ በደህና ተገላገለች። ልጁ እንደተወለደ ወይዘሮ አዳነች እትብቱን ቆርጠው ከቋጠሩ በኋላ ቀሪውን እትብትና የእንግዴውን ልጅ አቶ ረዳ ከጓሮአቸው ቀበሩት። አንዳንድ የግል ቁሌና ዛር አዲስ ሕፃን ሲያለቅስ በመስማት በአካባቢው ሊያንዣብቡ ይችሉ ይሆናል ብለው ቅማንቶች ይገምታሉ። በተለይ ፀሐይ መጥፎ የሆነ ቁሊ ወደ ሕፃኑ አጠገብ ሊመጣ ይችላል ብላ ስለሠጋች ቁሌው እንዲርቅ ለማባበል አንድ ዶሮ በማረድ መስዋዕት ተደረገለት። የታረደውን ዶሮ ወጥ ሠርተው ሕፃኑ ሲወለድ ለነበሩት ሰዎች ግብዣ አደረጉላቸው። በተጨማሪም በማዋለድ ረገድ የረዱ ሰዎች ሁሉ እንደውለታ ተቆጥሮላቸው ሌላ ቀን አንድ ጥሩ የምግብ ግብዣ ይኖራቸዋል።

ፀሐይ ወንድ ልጇን ይዛ ወደምትገለልበት ጐጆ (ከሳ) ገባች። ልጁ የተወለደበት ዋናው ቤት እንዲነፃ ወምበሩ በደገሙበት ቀኖና (ፀበል) በቤቱ ዙሪያና በማዋለዱ ተግባር በተካፈሉት ሴቶች ላይ ተረጨ። በሰባተኛው ቀን ፀሐይ ጐጆውን ከመልቀቋ በፊት ሰውነቷን ታጠበች፤ እንዲሁም እራሷን ተላጭታ ንፁህ ልብስ ለበሰች። ከዚያም የነበረችበት ጊዜያዊ ጐጆ በጣም ረክሷል በሚል ምክንያትና እንደሌላው የወር አበባ ጊዜ እንደሚጠቀሙበት ጐጆ መልሰው እንደገና ስለማይገለገሉበት ከፀሐይ አሮጌ ልብስና አንዳንድ በጐጆው ውስጥ ስትጠቀምባቸው ከነበሩት ቁሳቁሶች ጋር እንዲቃጠል ተደረገ። በመጨረሻም ፀሐይ ነፅታለች ተብላ ከባለቤቷ ከቢተው ጋር እንደገና ተቀላቀለች።

# «ቀኖና»፣ ወደቅማንት ኅብረተሰብ አባልነት ለመሸጋገር የሚደረግ ሥርዓተ-ቅዳሴ

የቅማንት ኅብረተሰብ አካል እንዲሆኑ ሕፃናት በተወለዱ ከሃያ እስከ ሠላሣ ቀን ባለው ጊዜ «ቀኖና» የተባለው ሥርዓተ-ቅዳሴ እንዲከናወን ሃሣብ ይቀርባል። የወምበሩ መገኘት አስፈላጊ ባይሆንም ሥነሥርዓቱ እንዲካሄድ ግን የሚፈቅደው እራሱ ነው። የፀሐይና የቢተው ልጅም ከዚህ ባልተለየ መልኩ ቴስ ጸሎት እንዲያደርሱ ተደርጐ በገበቴ (የእንጨት ሳህን) በተሞላ ቀኖና በተባለው ፀበል ተነከረ። ልጁ በፀበሉ ተነክሮ እንደወጣና አዲስ ልብስ እንደለበሰ የቅማንት ኅብረተሰብ አባል መሆኑ ተረጋገጠ ማለት ነው። በወቅቱ ለልጁ የተለያዩ ስሞች ይሰጡታል። አንደኛው ስም የሃይማኖት ስም ሆኖ በክብረ-በዓል ሥነሥርዓቶች ጊዜ የሚጠቀምበትና የስው ደረጃ የተሰጠው ለመሆኑ ማረጋገጫ ነው። በዚህም መሠረት ፀሐይና ቢተው የልጃቸው የዘውትር ስም ወልዱ እንዲሆን ወሰኑ።

በመሠረቱ ቀኖና ፀበል ከመነከር ጋር አብሮ የሚሄድ የማዕዳት ሥርዓተ-ቅዳሴ ነው። አንዳንድ ክርስቲያኖች ከሥርዓተ-ጥምቀት የተወሰደ ሥነሥርዓት ነው ቢሉም ይህ ግን ከጥምቀት ጋር ግንኙነት እንደሌለው ነው የምንገነዘበው። ቅዱስ ፀበሉ ሕፃኑን በማንፃት ወደ ቅማንት ኅብረተሰብ እንዲቀላቀል የሚያደርገው ነው። እንዲሁም ትላልቅ ሰዎች «ከረከሱ» በዚህ ዓይነት ሥርዓተ-ቅዳሴ እንዲነፁ ይደረጋል። አንድ ሰው ረከሰ ወይም ተበከለ የሚባለው ረቡዕ፣ አርብ ወይም ቅዳሜ እለት እንስሳት ካረደ፣ አንዲት ሴት አደፍ ሆና ሰባት ቀን ሳይሞላት ከጐጆዋ ከወጣችና ከወለደች በኋላም ለሰባት ቀናት ካልተገለለች፡ እንዲሁም ማንኛውም ሰው በጅብ ከተነከሰ ይረክሳል ተብሎ የሚታሰበውን የመሳሰሉትን ያጠቃልላል። እስካሁን የታወቀ ሁኔታ ባይኖርም እስላሞች ወይም ክርስቲያኖች የቀኖና ሥነሥርዓት በመፈፀም የቅማንት ኅብረተሰብን ለመቀላቀል እንደሚችሉ ነው።

ከጥቂት አሥርተ ዓመታት በፊት አንድ ቅማንት ያልሆነ ሰው ወደ አንድ ቅማንት ቤት ከሄደ ቤቱና እንግዳው የተጠቀመባቸው ዕቃዎች ረክሰዋል ስለሚባል ለማንፃት ይህን ሥነሥርዓት ማካሄድ ያስፈልጋል። ቀኖና ከመደረጉ በፊት ቤቱን

ጠርገው ያፀዱታል፣ እንዲሁም እንግዳው የተጠቀመባቸው ዕቃዎች በሙሉ ይታጠባሉ። ይህ እምነት የቅማንቱ ኅብረተሰብ ከሌላው ኅብረተሰብ ጋር ወዳጅነትና ማኅበራዊ ግንኙነት እንዳይመሠረት አጥር ሆኖ ቆይቷል። ሆኖም የማንፃቱ ሥነሥርዓት ማኅበራዊ አጥር በ1880ዎቹ አንዳንድ ቅማንቶች የክርስትናን ሃይማኖት እንዲቀበሉ ሲደረግ መፈራረስ ጀመረ። ይህም በዝምድና በመተሳሰር የጥንቱ የብቸኝነት አስተሳሰብ እየተዳከመ ስለመጣና ከዘመዳሞች መካከልም ከፊሎቹ ክርስትናን ስለተቀበሉ ግንኙነቱም የግድ አስፈላጊ በመሆኑ ከሌላው ኅብረተሰብ ጋር መገናኘት መበከልን ያስከትላል የሚለው አስተሳሰብ እየተረሳ መጥቷል።

## ልጅ አስተዳደግ

የቅማንት ሕፃናት አድገው መሄድና መናገር እስከሚችሉና ዕድሜያቸው በግምት ሁለት ዓመት እስኪሞላቸው ድረስ የሞግዚት እንክብካቤ ይደረግላቸዋል። በዚህ ጊዜ ውስጥ አንድ ሕፃን ልጅ በእናቱ ታቅፎ ስለሚያድግ የደኅንነቱ ሁኔታ ይጠበቃል፣ የእናቱንም ፍቅር ያገኛል። አንዳንድ እናቶች አልፎ አልፎ ሕፃኑን ያስተኙታል፣ ሲያለቅስ ደግሞ አንስተው ጡት ያጠቡታል። ብዙዎቹ እናቶች ግን ሕፃኑን ከጉያቸው ሳያወጡ እንደልቡ እየተፈራገጠና የእናቱን ጡት እየጠባ እንዲያድግ ያደርጋሉ።

ቀለጤው ሕፃን ወልዱም አስተዳደጉ በዚህ መልክ ነበር። ከዚህ በተጨማሪ ወልዱ ሁለት ዓመት እስኪሞላው ድረስ እናቱ ፀሐይ ወይም በቤተሰቡ ያሉት ሴቶች በአንቀልባ ጀርባቸው ላይ በማዘል ይንከባከቡታል። አንቀልባውን ሴቶች መንገድ ሲሄዱ፣ በቤት ውስጥና በእርሻ ሥራ ላይ ሲሠማሩም ልጃቸውን ያዝሉበታል።

ቅማንቶች «ፍቅር ወደታች እየወረደ ይሄዳል» የሚል አባባል አላቸው። ይህም የሚባለው አንድ አዲስ ሕፃን ልጅ በተወለደ ቁጥር የአዲሱን ሕፃን የፍቅር ፍላጎት ለማሟላት ሲባል ወላጆችና ዘመዶች ለታላቁ ሕፃን ልጅ ያሳዩት የነበረውን ፍቅር ቀስ በቀስ ስለሚቀንሱ ነው። ሌላ ልጅ ከተወለደ ወይም አንድ ልጅ ሦስት ዓመት ከሞላው መታቀፉና ጡት መጥባቱ ይቀርበታል፣ ይህም በድንገት ወይም ቀስ በቀስ የሚደረግ ነው።

ልጁ ጡት እንዲተው እንደ እሬት የመሰለ መራራ ቅጠል ወይም እበት ጡቱን በመቀባት መከላከል ይቻላል። አንዳንድ ጊዜም እናትና ልጅ እንዳይገናኙ በማገለልም ይፈጸማል።

ጡት የማስተው ጊዜ እየተቃረበ ሲመጣ ሕፃኑ አልሚ የሆነ ደረቅ ምግብ መብላት ይጀምራል። ይህ ሁኔታ አንድ ሕፃን ልጅ ድሮ ሲያገኝ ከነበረው ከእናቱ ሙቀትና ፍቅር መገለልን ስለሚያስከትልበት በተለይ ተፎካካሪ ሕፃን ካለ ጡት ማስተው ለልጁ አስደንጋጭና የሚያበሳጨው ይሆናል። ከሌሎች ትናንሽ ልጆች ጋር እንዲተኛ ከተደረገ በኋላ ሌላ ሕፃን ኖረ አልኖረ ተነስቶ ወደ እናቱ ጉያ ለመግባት ወይም በእንቀልባ ለመታዘል የሚሞክርበት ጊዜም አለ። ሕፃን ልጅ ሲተኛ ሙሉ በሙሉ በእናቱ ጉያ ተሸፋፍኖ ነው፤ ለብቻው መተኛት ሲጀምርም እናቱ በሚገባ ከእግር እስከራሱ በጋቢ ወይም በሌላ ጨርቅ ተሸፋፍኖ መተኛቱን ትቆጣጠራለች። ያደጉ ልጆችና ጉረምሶችም ልክ ልጆች በነበሩበት ጊዜ በአገኙት ልምድ መሠረት ከእግር እስከ ራሳቸው በጋቢያቸው ተጠቅልለው ነው የሚተኙት።

# በልጅነት የሚገኝ ልምድ

ለአንድ የቅማንት ልጅ ከሕፃንነቱ ጀምሮ ስለሚሰጠው ሥልጠና ነጋሽ የተባለው የቢተው ታላቅ ወንድም ልጅ፣ አራት ዓመት የሆነው ታደሰ፣ ያለፈበትን ሁኔታ እንደምሳሌ እንውሰደው። ታደሰ ጡት ማቆም እንደጀመረ አፍቃሪዋ እሚታው (አያት) ወይዘሮ አዳነች ትንሽ ምግብ በቆለምሸሽ በማቅረብ ከሌሎች ልጆች ጋር ሆኖ የአበላል ሥነሥርዓት ያስተምሩታል። እንደሌሎች ሕፃናት ብዙ ወተትና የወተት ተዋፅዖች እንዲመገብ ይሰጠዋል። ከሚሰጠው መደበኛ ምግብ በተጨማሪ ምግብ እንዲሰጠው ከጠየቀ ወይም ካለቀሰ አይከለከልም፣ ይሰጠዋል።

ጡት በሚተውበት ወቅት ታደሰ ሳያሰልስ ስለሥነም ግባር፣ ሰውን ለማክበር የሚደረጉ ነገሮችን ለምሳሌ የታላቆቹን ጉልበት መሳም፣ አንዳንድ አባባሎችን፣ ለመጥቀስ ያህል፣ «ደህና ዋላችሁ» (ቴናሊየን) እና «አመሰግናለሁ» (አዲራሊየን) ማለትን እንዲያውቅ ይደረጋል። እንደ ታደሰና ወልዱ ያሉ ሕፃናት በቤት ውስጥ ሲርመሰመሱና ሲንከባለሉ ሊውሉ ይችላሉ፤ ነገር ግን ዕቃ መስበር ወይም ማበላሸት አይፈቀድላቸውም። አንድ ልጅ መጥፎ ጠባይ

ኮሶው ብዙ ጊዜ ቅጣቱ የቃል ነው፡፡ ታደስ፣ ወንድሞቹ ጓሉና ወርቂ ጥፋት ሲያጠፉ ከሚደርስባቸው ስድብ ወይም ማስፈራሪያ «ጅቡ ይበላሃል»፣ «ሽፍታው ይጉዳሃል» የሚሉ አባባሉች ይገኙበታል፡፡ በሌላ ጊዜም ቁንጥጫ፣ ጥፊ ወይም በምግብ መቅጣት በወላጆች የሚወሰዱ እርምጃዎች ናቸው፡፡ ሦስቱ ወንድማማቾች ጠባያቸውን እንዲያሳምሩ የቁልምጫ ምግብና መጠጥ መስጠትም የተለመደ ነው፡፡

ወጣት ወንዶችና ልጃገረዶች አንድ ላይ ሆነው መጫወት ስለማይከለከሉ ታደስ ከልጃገረዶች ጋር ይጫወታል፣ ይደባደባል፣ ነገር ግን ከፈቃደ-ሥጋ ጋር የተያያዘ ጨዋታ አይፈቀድም፡፡ ጉረምሳ ወንዶችና የደረሱ ልጃገረዶች በአንድ ላይ መተኛትም ክልክል ነው፡፡ ስለ ግብረ-ሥጋ ግንኙነት ብዙ ጊዜ በቤት ውስጥና ሰው በተሰበሰበበት ቦታ ላይ መነጋገር እንደ ነውር ስለሚቆጠር ወጣቶች ስለዚህ ጉዳይ ብዙ ጊዜ ቀስ በቀስ ግንዛቤ ለማግኘት የሚችሉት ትላልቅ ወንዶች የሚያደርጉትን የእርስ በእርስ ውይይት በማዳመጥ ነው፡፡

የንጽሕና አጠባበቅ ትምህርት በቅማንቶች ዘንድ መስጠት ከሚገቡት ትምህርቶች ዋነኛው ነው፡፡ ታደስ ምግብ ከመብላቱ በፊትም ሆነ ምግብ በማዘጋጀት በሚረዳበት ጊዜ እጁን መታጠብ እንዳለበት እንዲያውቅ ይደረጋል፡፡ ታላቅ ወንድሙ ወርቂም እንጀራ መብላትና ከሞሰቡም እንጀራ መቁረስ ያለበት በቀኝ እጅ መሆኑን ግራ እጁን በጥፊ እየተመታ እንዲማር ይደረጋል፡፡ እንዲሁም በወር ወይም በሁለት ወር አንድ ጊዜ ልብሳቸውን እንዲያጥቡ ምክር ይሰጣል፡፡

ታደስና ወልዱ መቼና የት ሽንትና ዓይነ-ምድር መፀዳዳት እንዳለባቸው በመሠረቱ ትምህርት አይሰጣቸውም፡፡ ወልዱ ዕድሜው ከሁለት ዓመት በታች በመሆኑ ሁለቱንም ከቤት ውስጥ ቢያደርግ ቁጣ አይደርስበትም፡፡ እያደገ በሄደ ቁጥር ግን የሚፀዳዳው ከቤቱ እየራቀ እየሄደ ነው፡፡ ጉረምሶችና ትላልቅ ሰዎች ሽንታቸውን ከቤት አጠገብ ለመሽናት ቢችሉም ለዓይነ-ምድር ግን ወደ ጫካና ሜዳ መሄድ ይኖርባቸዋል፡፡

# በወጣትነት ሙያዊ ሥልጠና

አንድ ልጅ ወደፊት ሊተዳደርበት ባሰበው የሙያ መስክ እንዲለማመድ ዝግጁ ማድረግ ተገቢ ነው። ይህ ዓይነት ዝግጅት በልጅነት በጨዋታ መልክ ነው የሚጀመረው። ታደሰና ጓሉ በእንጨትና በጭቃ የጨዋታ ቤት ይሠራሉ፡ በትራቸው ላይ በመንፈራጠጥ ፈረስ መጋለብ ይለማመዳሉ፡ እንዲሁም በሹል እንጨት እርሻ ማረስ ይሞክራሉ። ጓሉ በበትሩ እርፍና ሞፈር እያዘጋጀ ታደሰ እንደበሬ ሆኖ እንዲጐትት ያደርገዋል። ታደሰ ወልዱን አንድ ቀን «እንደበሬ እጠምድሃለው» ይለዋል። ይህንን የሰሙት ወይዘሮ አቦነሽ «እንደዚህ ብታደርግ ጉንጮችህን በቁንጥጫ እንሳልሃለሁ» እንዳሉት አስታውሳለሁ። የመጫወቻ የበሬ ጅራፍ ከእንጨትና ከልጥ መሥራት የተለመደ ነው። እንደወርቄ ያሉ የአምስት ዓመት ልጆች ከእሱ ከፍ ካሉ ልጆች ጋር ተጃ ጥበቃ በመውጣት በሥራው ላይ ሆነው የእረኝነቱን ሥራ ይለማመዳሉ። አንድ ሃያ ኪሎ ግራም የሚመዝን ልጅ አንድ ሺህ ኪሎ ግራም የሚመዝነውን በሬ (ምንም ፍንክች ባይልለትም) በዱላ ሲመታው ማየት አዲስ ነገር አይደለም።

ወጣት እረኞች የሚበላ እሸት ካገኙ የማንም ይሁን የማን ባለቤቱ ሳያያቸው ቀጥፈው ይበላሉ። ይህ አጋጣሚ ነው ትናንሽ ልጆችን ከእናታቸውና ከምድጃቸው እርቀው ወደ እረኛነቱ የሚጐትታቸው። ወርቄ ዕድሜው አሥራ ሁለት ዓመት ሲሆን ከጐረቤት የእርሻ ቦታ እሸት እየሰረቀ በማስቸገሩ አንድ የተናደደ ገበሬ «ከብቶች እህሌን እንዳይበሉ በአጥር እየተከላከልኩ ቢሆንም ወርቄ የተባለ ልጅ እንደ ዝንጀሮ አጥር እየዘለለ እየገባ ነው። ግድየለም አንድ ቀን ከወርቅ የበለጠ ካሣ ይከፍላታል» ብሎ በማማረር መፎከሩን አስታውሳለሁ።

ወጣት ልጃገረዶች አፈር እየፈጩ በማቡካት የውሸት እንጀራ በመጋገር ይለማመዳሉ። ከሦስት ዓመታቸው ጀምሮ ዶሮ ከመጠበቅ አልፈው እስከ ዕቃና እንጨት ማቅረብ ሥራ ላይ ይደርሳሉ። ከዓመትና ከሁለት ዓመት በኋላም የመላላኩን ሥራ ይያያዙታል።

ልጆች ስምንት ዓመት ሲሞላቸው በማንኛውም ዓይነት ሥራ በመሳተፍ ወላጆቻቸውን ይረዳሉ። ልጃገረዶች ወፍጮ

ይፈጫሉ፣ ቤት ያፀዳሉ፣ ከዶሮና ከሥጋ ወጥ በስተቀር ሌላውን ምግብ ሁሉ ማብሰል ይችላሉ። ወንዶች ልጆች ደግሞ ከአባታቸው ጋር ወደ ገበያ በመሄድ፣ ቤት በመሥራትና በእርሻውም ቦታ አንዳንድ ሥራዎችን በመሥራት ይረዳሉ። አንዳንድ ጊዜ ነጋሽ ማንኛውም አባት እንደሚያደርገው ሁሉ ልጁ ወርቁ በሬዎችን ጠምዶ ትንሽ ሾርችን እንዲያርስ ይፈቅድለታል። በመጀመሪያው የጉርምስና እና የኮረዳነት ጊዜያቸው ወንዶችና ሴቶች ልጆች ለሕይወት አስፈላጊ የሆኑትን ነገሮች ለመሥራት የሚያስችላቸውን ዕውቀት ይጨብጣሉ። ለወላጆቹም ሆነ ለልጆቻቸው ደህንነት ሲባል ልጆቹን ገና በወጣትነታቸው ኑሮ ምን እንደሚመስልና እንዴት መቋቋም እንዳለባቸው ማስተማር ጠቃሚ መሆኑን ያውቃሉ። ይህ ከሆነ አንድ ሰው እርጅና ሲመጣ ጠንካራና በቂ ችሎታ ያላቸው ወንዶች ልጆችና ያገቡ ጠንካራ ሴቶች አጋር ይሆኑለታል ማለት ነው። በዚህ ረገድ አቶ ረዳ የታደሉ ናቸው። ጥሩ አቋም ባላቸው ሦስት ጉልበታም ልጆቻቸው እየተረዱ በራሳቸውና በባለቤታቸው የዘር ሐረግ ያገኙዋቸውን መሬቶች አገላብጠው ለማረስ አስችሏቸዋል። ብዙ የምርት ውጤት ለአቶ ረዳ ብዙ ሀብትና ኃይል ማለት ሲሆን አንድ ልጅ ብቻ ቢኖራቸው ኖሮ ይህን ያህል አያምርቱም፣ ምንም ልጅ ባይኖራቸው ደግሞ ጠቅላላ ውድቀት ይሆንባቸው ነበር።

## አልባሳትና ጌጣጌጥ

እንደ ታደሰ ያሉ የአምስትና የስድስት ዓመት የቅማንት ሕፃናት ከፊል ሰውነታቸውን ራቁታቸውን እንዲሄዱ ቢፈቀድላቸውም ከዚህ ዕድሜ በኋላ ግን ሁልጊዜ ልብስ መልበስ ይኖርባቸዋል። ትናንሽ ወንዶች ልጆች ጥብቆ ብቻ፣ ልጃገረዶች አንድ ወጥ ቀሚስ፣ ከፍ ያሉ ልጆች ደግሞ ረዥም ቁምጣ ይለብሳሉ። ወርቁና ታላቁ የሆኑት ዘመዶቹ ከእጀ ጠባብ ጋር ቁምጣ ሱሪ ወይም ባት-ተሁለት ወይም ረዥም ሱሪ በቀበቶ ወይም በሸምቀቆ ይታጠቃሉ። ባርኔጣ ወይም ቆብ ብዙም አልተለመደም። ከዚሁ ላይ ነጭ ጋቢ ወይም ኩታ ደርቦ መሄድ የተለመደ ነው። አንዳንድ ጉረምሶች ጋቢውን በሸሚዝ ምትክ ይለብሱታል። የበግ አጐዛና ብርድ ልብስ በሰውነት ላይ ጣል አድርጐ መሄድም አለ። ወይዘሮ አዳነችና ምራቶቻቸው አንድ ወጥ ቀሚስ ከመቀነት ጋር ያደርጋሉ፤ እንዳስፈላጊነቱም ኩታ በላዩ ላይ ይደርባሉ። አንዳንድ ጊዜ ቀሚሱ ይጠለፋል፣ ኩታውም

ቆንጆ ጥለት ሊኖረው ይችላል። ከቆዳ ወይም ከጉንደር ከተማ የሚገኝ ከመኪና ጉማ የተሠራ ነጠላ ጫማ ማድረግ ከቅርብ ጊዜ ወዲህ በአንዳንድ ሰዎች እየተለመደ መጥቷል።

ልጆች በሰማያዊ ዶቃና ዛጉል ያጌጠ ማተብ በአንገታቸው ላይ ያደርጋሉ። ልጃገረዶች ደግሞ ከመዳብ ወይም ከብር የተሠሩ የእጅ አምባርና ባለዶቃ የእግር አልቦ ያጠልቃሉ። ከዚህም በስተቀር ሴቶችም ሆኑ ወንዶች የብር ወይም የመዳብ ቀለበት በጣታቸው ያደርጋሉ። ከአሸን ክታቡ ጋር የኢትዮጵያን ወይም የእንግሊዝ ወይም የጣልያን ሳንቲሞች በገመድ ተንጠልጥለው በአንገት ላይ በማጥለቅ ለጌጥነት ያገለግላሉ።

ከብ የብር ጉትቻ ለማድረግ ሴቶች ጆሮአቸውን ያስበሳሉ። ከአምሣ ዓመት በፊት ወንዶችም የጆሮ ሎቲ ያደርጉ ነበር። ንቅሳት አንዱ የመጋጌጫ ስልት ሲሆን ንቅሳቱ በአንገት፣ በድድ፣ በደረት፣ በግንባር፣በእጅና በቁርጭምጭሚት ላይ ሊሆን ይችላል። ቅብዓ-ኑግ ከጥቀርሻ ጋር ተቀላቅሎ እንዲሞቅ በማድረግ ማትለሚያ ከተዘጋጀ በኋላ በግራር ወይም በአጋም እሾህ ማቅለሚያውን በማጣቀስ በተፈለገው የሰውነት ክፍል ላይ በመጨቅጨቅ ንቅሳቱ ዝግጁ ይሆናል። ንቅሳት ከጌጥነቱ በተጨማሪ ለበሽታ ፈውስና መከላከያም ሆኖ ያገለግላል። በአንገት ላይ ንቅሳት ሲደረግ እንቅርትን እንደሚያድንና ድድን መንቀስ ደግሞ የጥርስ መድማትንና ቁርጥማትን ያስቀራል ይባላል። እንደ ፀሐይና አልማዝ ለመሳሰሉት ቆንጆጅት ደግሞ ቡዳ እንዳይበላቸው ንቅሳት ጥሩ መከላከያ መሆኑ ይነገራል።

ወልዱን የመሳሰሉ ትናንሽ ልጆች የተለየ የፀጉር አያያዝ ስልት የላቸውም። አራትና አምስት ዕድሜ ያላቸው እንደ ታደሰ ያሉት ልጆች ፀጉራቸውን ተላጭተው ትንሽ ቁንጮ ብቻ ከአናታቸው ላይ ይተዋል። አሥር ዓመት ሲሞላቸው እንደ ወርቂ ሙሉ በሙሉ ፀጉራቸውን ይላጫሉ። ዕድሜያቸው አሥራ ስምንት ዓመትና ከዚያም በላይ የሆነ እንደ ነጋሽ ያሉ ጉረምሶች በመሰሎቻቸው ዘንድ እንደተለመደው ሁሉ ፀጉራቸው አጠር ያለ ሲሆን እንደ አቶ ረዳ ጠና ያሉ ሰዎች ግን በጣሊያን ወረራ ዘመን (እ.ኤ.አ. ከ1935-1941 ዓ.ም.) አርበኞች ያደርጉት እንደነበረው ፀጉራቸውን ያጐፍራሉ።

እንዲት ልጃገረድ አራት ዓመት ሲሞላት ፀጉሯ እንዲያድግ ይደረግና ከራስ ቅሏ በስተጀርባ ትንሽ ቦታ ተላጭቶ ዙሪያውን ሹሩባ (ጋሚ) ትሠራለች፡ ስምንት ዓመት ሲሞላት ደግሞ መሐል ላይ የተላጨው ይተውና እንዲያድግ ተደርጉ ሳዱላ ይሆናል፡፡ እንዲት ሴት አግብታ ለብዙ ጊዜ ከቆየች በኋላ ፀጉሯ ሙሉ በሙሉ እንዲያድግ ይደረግና ሹሩባ (ቁንዳላ) ትሠራለች፡፡ ጠና ያለች ስትሆን ደግሞ እንደ ወንዶች ፀጉሯን ታሳጥራለች፡፡ ይህን ዓይነት የፀጉር አያያዝ ሀዘንተኛ ሴቶችም ይጠቀሙበታል፡፡

የቅማንቶች ልብስ አለባበስ፣ የፀጉር አያያዝና ጌጣጌጥ አደራረግ በቤጊምድርና ስሜን ከሚኖሩት አማራና ፈላሻዎች ጋር አንድ ዓይነት መሆኑን መገንዘብ አያስቸግርም፡፡

## ጋብቻና የጉርምስና ጊዜ

በተለይ የቅማንትን የጋብቻ ሁኔታ ለመረዳት እንዲያስችለን የነጋሽና የቢተው ታናሽ ወንድም የሆነው የአቶ ረዳ ልጅ መልኬ ቆንጆዋን ከበቡሽን ሲያገባ የተደረገውን የጋብቻ ሥነሥርዓት በኋላ እንመለስበታለን፡፡ አስቀድሞ ግን የቅማንት ጋብቻ በአጠቃላይ እንዴት እንደሆነ እናያለን፡፡ ልጃገረዶች ገና በወጣትነታቸው አንዳንድ ጊዜ ሰባት ዓመት ሲሞላቸው በአብዛኛው ግን ከስምንት ዓመት እስከ አሥራ አምስት ዓመታቸው ባለው ጊዜ ውስጥ ይዳራሉ፡፡ ከጋብቻ በፊት የግብረ-ሥጋ ግንኙነት ስለማይፈቀድ የሴቶች ክብረ-ንጽሕና አለመደፈር ለጋብቻ ወሳኝ ነገር ነው፡፡ ይህም በመሆኑ እንዲት ሴት ፈት ካልሆነች በስተቀር ድንግልነቷ ካልተጠበቀ ባል በቀላሉ አታገኝም፡፡ በሴቶች ዘንድ ከጋብቻ ውጭ የሚደረግ የግብረ-ሥጋ ግንኙነት የተከለከለ ስለሆነ በጋብቻ ጊዜ ነገሩ ከተደረሰበት ለፍች ያደርሳል፡፡ ከጋብቻ በፊትም እርግዝና የተወገዘ በመሆኑ ብዙ ጊዜ አይከሰትም፡፡ ጋብቻ የሚፈጸመው በልጅነት በመሆኑ ልጅ የሚፀነሰው ጋብቻው ከተፈፀመ ከጥቂት ዓመታት በኋላ ነው፡፡

ዕቁባት ማስቀመጥ ቢፈቀድም ብዙ የተለመደ አይደለም፡፡ ሊፈቀድ የሚችለውም አንድ ያገባ ሰው ሚስቱ ለአካለ መጠን ያልደረሰች ከሆነ ነው፡፡ እንዲት ድሀ ልጃገረድ በሀብት ማነስ ምክንያት ዘመዶቿ ሳይድሯት ሲቀሩና ከዝቅተኛ ቤተሰብ በመምጣቷ ባል የማግኘት ዕድሏ የተመናመነ ከሆነ ምርጫዋ

ከአንድ ሀብታም ቤት ገብታ በግርድና መቀጠር ይሆናል። በዚህ ጊዜ የአሳዳሪዋ ወንድ ልጅ (ያገባም ሆነ ያላገባ) ወሽሜት ልጅ ልትወልድ ትችላለች። ያለችበትን ቤተሰብ ከለቀቀች ልጁን ከአባቱ ዘንድ ጥላው ትሄዳለች። ጥንት የባሪያ አሳዳሪ ሥርዓት በሰፈነበት ዘመን አንድ ሰው ከባሪያው ጋር የግብረ-ሥጋ ለመፈጸም ይችል እንደነበረ ቢታወቅም፣ ሴተኛ አዳሪነት ግን በቅማንት ዘንድ ፈጽሞ አይታወቅም።

ወንዶች ከአሥራ ስምንት እስከ ሃያ ዓመት ድረስ ባለው ዕድሜያቸው በአብዛኛው ጋብቻ የሚፈጽሙ ቢሆንም የጋብቻው ጊዜ እስከ ሠላሣ ዓመት ዕድሜ ድረስ ሊራዘም ይችላል። ከጋብቻ በፊት የግብረ-ሥጋ ግንኙነት ለማድረግ የወንዶች እድል የጠበበ ነው፣ ነገር ግን አልፎ አልፎ ጠና ካሉና ባሎቻቸው ከሞቱባቸው ሴቶች ጋር ድርጊቱን ይፈጽማሉ። አስገድዶ መድፈር በቅማንቶች ዘንድ አይዘወተርም፣ ግብረ ሰዶምም ቢሆን አንዳንድ ጊዜ በእረኞች መካከል ሊከሰት ይችል ይሆናል እንጂ ብዙ አይታወቅም።

የቅማንት ጋብቻ በዘልማድ በሙሽራውና በሙሽሪት ወላጆች መካከል በሚደረግ የቃል ውል መሠረት የሚፈጸም ነው። የመሬት አለኝታና ሌላም ሀብት በጋብቻ ጊዜ ወሳኝነት ስላለው በሙሽራውና በሙሽሪት ቤተሰቦች መካከል በሚደረገው የስምምነት ውል የሚገለጽ ጉዳይ ነው። ጋብቻው (ፋሁ የዊናት) እና ሠርጉ (ስናው) ለአንድ ወንድ ቅማንት ከኩረምሳነት ወደ ጉልማሳነት የሚያሸጋግረው ድልድይ ነው። ሴቶች ግን ገና ወጣት ስለሆኑ ሁልጊዜ ወደዚህ ደረጃ ተሸጋገሩ ማለት አያስደፍርም። ለወንዶችም ሆነ ለሴቶቹ ለዚህ ደረጃ በመብቃታቸው ሌላ የተለዩ ሥነሥርዓት አይከሄድላቸውም።

## በጋብቻ ወቅት የሚደረግ የሀብት ዝውውር

ሙሽራውና ሙሽሪት ለኑሮአቸው ማጫ(መቋቋሚያ) እንዲሆንላቸው ወላጆቻቸው በየበኩላቸው የገንዘብና የእንስሳት መዋጮ በማድረግ ይሰጧቸዋል። መጠኑም አስቀድሞ በተስማሙበት የቃል ውል መሠረት ይሆናል። አንዱ ወገን ከፍ ያለ ማጫ ሌላው ደግሞ ዝቅ ያለ ማጫካቀረበ፣ ፍች

በሚያጋጥምበት ወቅት እሱ ወይም እሷ ልዩነቱን የመውሰድ መብት በቃል ውላቸው ላይ የተጠበቀ ይሆናል።

የጥንቱ የጋብቻ የባህል ትውፊት ደግሞ ጋብቻ ከመፈጸሙ በፊት ለሙሽራይቱ እጅ መንሻ (መታያ) የሚሆን የኢትዮጵያ ብር ከ7.50 እስከ 20 ማሪያ ቴሬዛ ብር መክፈል አስፈላጊ ነበር። የሙሽራው ቤተሰቦች አቅማቸው ከፍተኛ ከሆነ በዚያው መጠን ክፍያውን ከፍ ማድረግ ይችላሉ። እጩው ሙሽራና አባቱ ለሙሽራይቱ ወላጆች ለእጅ መንሻ የሰጡት ገንዘብ እንደገና ተመልሶ ለባለትዳሮቹ በሁለት ዓይነት መልክ ለመቋቋሚያ የሚሰጥበት መንገድ አለ። የመጀመሪያው በሠርጉ ድግስ ማብቂያ ላይ ሙሽራው የጀግና ፉከራ አሰምቶ አማቶቹ በመደሰት በሽልማት መልክ ገንዘቡን የሚመልሱበት ሁኔታ ያለ ሲሆን በሌላ በኩል ደግሞ የሙሽራዋ አባት ለምንጣፍ የሚሆን ጀንዲ (ሌማት) የተለያዩ እቃዎችና እንዲሁም ሙሽራዋ በግል የምትጠቀምበት በአረብ (ቆዳ) የተለበደ አገልግል በልዩ ልዩ ሰቃዎች ተሞልቶ መስጠት የተለመደ ነው። እንዲያውም የመታያው ገንዘብ ለዚህ ጉዳይ በቂ ሆኖ ካልተገኘ የሙሽራይቱ አባት ከራሱ ገንዘብ የሚጨምርበት ጊዜም አለ። ጥንት ቅማንቶች ጋብቻው የጠነከረና የሰመረ እንዲሆን ሀብታቸውን ወደልጆቻቸው ማስተላለፍ አስፈላጊነቱን ስለሚያምኑበት የእጅ መንሻው ከፍተኛ እንደነበረ ታውቋል። በአሁኑ ጊዜ ግን መታያው ለስሙ ያህል የሁለቱን ቤተሰቦች ትስስር በሚያጠናክር መልክ ከበጐ ፈቃድ መግለጫነት የሚያልፍ አይደለም።

አንድ ሰው ከጓደኞቹ ጋር በመሆን አንዲን ልጃገረድ አስገድዶ በመጥለፍ ጋብቻ መፈጸም ብዙም የተለመደ አይደለም። ሆኖም ግለሰቡ አንዲት ልጃገረድ ለማግባት ፈልጉ ድሃ በመሆኑ ምክንያት የልጅቷ ወላጆች ጋብቻውን ቢከለክሉት ጠለፋ ሊካሄድ ይችላል። በጠለፋ ምክንያት በቤተሰቦች መካከል ግጭት እንዳይፈጠር የቅማንት ቄሶችና ሽማግሌዎች በጠላፊው ላይ የገንዘብና የክብት ቅጣት በመጣል የልጅቷ አባት እንዲካስና በኅብረተሰቡ ዘንድ ክብሩ ተጠብቆ እንዲቆይ ለማድረግና ሁኔታው እንዳይባባስ ይከላከላሉ። ይህ የሀብት ዝውውር ወይም ቅጣት ሳይሆን በመሠረቱ አባትዬው ለተጋቢዎች የሚመልሰው ነው። ዋናው ቁምነገር ግን የልጅቷ አባት መልካም ዝና እንዳይጉድፍ ለደረሰበት በደል ሥርዓት በያዘ መልክ እንዲካስ ማድረጉ ነው።

## የባሕል (ሲቪል) ጋብቻና ሃይማኖታዊ ጋብቻ

አብዛኛውን ጊዜ ቅማንቶች በባህል (ሲቪል) እና ሃይማኖታዊ የጋብቻ ሥነሥርዓቶች የተሳሰራሉ፡፡ ሦስተኛው ዓይነት ትስስር ደግሞ ሴትና ወንድ በሁለቱም ፈቃደኝነት በአንድ ላይ መኖር ሲጀምሩ የሚያጋጥም ነው፡፡ ይህ ዓይነት ትስስር ለአጭር ጊዜ ሆኖ ከሁለቱም ወገኖች አንዱ በማንኛውም ጊዜ ሊያፈርሰው ይችላል፡፡

በባህል ጋብቻው የሃይማኖት ሥርዓተ-ቅዳሴ ሳያስፈልግ ሠርግ በመደገስ ብቻ የሚፈጸም ነው፡፡ ይህ ዓይነት ጋብቻ በሁለቱ ወገኖች የጋራ ስምምነት መሠረት ንብረታቸውን እኩል በመካፈል ሊያፈርሱት ይችላሉ፡፡ ነገር ግን ባልና ሚስቱ ጠና ያሉ ሆነው በካሣ ሥነሥርዓት አልፈው በአዛውንትነት የሚታወቁ ከሆነ መፋታት አይችሉም፡፡ በዚህ ሁኔታ የሚገኙ ባለትዳሮች አንደኛው እንኳን ቢሞት እንደገና ለማግባት የወምበሩን ፈቃድ ማግኘት አስፈላጊ ይሆናል፡፡ እንዲሁም እሷም ሆነች እሱ ካሁን በፊት በካሣ ሥነሥርዓት ያላለፉ ከሆነ ይህንኑ መፈጸም ግዴታ አለባቸው፡፡

በቅማንት ኅብረተሰብ ሃይማኖታዊ የጋብቻ ሥነሥርዓት የሚካሄደው በቀሳውስቱ ዘንድ በመሆኑ አልፎ አልፎ የሚያጋጥም ነው፡፡ አንድ ቄስ ለማግባት ሲፈልግ ከወምበሩ ፈቃድ ማግኘት ይኖርበታል፡፡ ከዚያም ከቄስ እድምተኞቹ ጋር በመሆን ወደ እጮኛው ቤት ይሄድና በሌሎች ቄሶች አማካይነት የቅዳሴ ሥነሥርዓት ከተካሄደ በኋላ ሙሽራዋን የሚያከብራትና የማይፈታት መሆኑን ቃለ መሐላ ይፈጽማል፡፡ ለሴቲቱ የካሣ ሥነሥርዓት ማካሄድ አስፈላጊ ቢሆንም አግቢው ቄስ ግን ቀደም ብሎ ክህነት ሲቀበል ሥነሥርዓቱ የተካሄደለት ስለሆነ በድጋሚ የካሣ ሥነሥርዓት አያስፈልገውም፡፡ በመሠረቱ አንድ ቄስ ሚስቱ ከሞተችበት ወምበሩን አስፈቅዶ ሌላ ማግባት አይከለከልም፡፡

## የመልኬና የከበቡሽ ጋብቻ

የሃያ ዓመት ዕድሜ ያለው ወጣትና መልከ መልካሙ መልኬ ዛሬ የአሥር ዓመት ዕድሜ ያላትን ቆንጆና ዓይነ አፋር የሆነችውን ከበቡሽን የሚያገባበት ቀን ነው፡፡ ከንጋት በኋላ ገና በማለዳው መልኬና ዕድምተኞቹ በነጫጭ ልብስ አሸብርቀው ወደ

ከበቡሽ ወላጆች ቤት የሚያመራውን ጠመዝማዛ የእግር መንገድ ተያያዙት። መልኬ ዘመድ አዝማድ በሆኑትና በሌሎች ከጋብቻው በፊት በተመረጡ ስምንት ሚዜዎች ታጅቦ ነበር።

ከዚያም መልኬና አድምተኞቹ ሽር ጉድ ከበዛበት የሙሽራይቱ መኖሪያ ቤት ደረሱ። ከሦስት ቀን በፊት ትልቅ ዳስ ተጥሎ የድርቆሽ ሣርና የባሕር ዛፍ ቅጠል ጉዝጓዝ ለሠርገኞች ተነጥፎል። በከበቡሽ ዘመዶች የሚጋገረው የትኩስ እንጀራ ሽታ፣ ቅመማ ቅመም ከበዛበት ምራቅ ከሚያስውጠው የወጥ ሽታ ጋር በአንድ ላይ ተቀላቅሎ «ኑ ብሉኝ! ኑ ብሉኝ!» የሚል ይመስላል። ውሾች በታረደው ከብት ቅሬት ላይ አንድ ጉን ይዘው ይራኮታሉ። ተገቢው ሥጋ ተቆራርጦ እየተመተረ ለወጥ ሠሪዎች ሲሰጥ፣ ለቁርጥ የሚሆነውን ደግሞ እየለዩ ያስቀምጣሉ፣ የማይረባውን ሥጋ ደግሞ ዓይናቸውን ተክለው ለሚቀላውጡት ውሾች ሲጥሉላቸው እየተጣሉ ሲናጠቁ ማየት ራሱን የቻለ ልዩ ትርዒት ነበር። ከላይ ክንፎቻቸውን እያርገበገቡ የሚያርፉት ጆፌ አሞራዎች ደግሞ የሠርጉ ግርግር ሌላ አዳማቂ ናቸው።

የመልኬ «አባት» እና «አሽከር» ሚዜዎች በከበቡሽ አባት ቤት በር ላይ ቆመው እንዳሉ አዝማሪው ማሲንቆውን እየመታ ግጥሞችን ይደረድር ነበር። በአገሩ ባህል መሠረት አባት ሚዜው ከሁሉም ሚዜዎች በዕድሜ የበሰለ ሲሆን ሥራው ሙሽራውን ማማከር ነው። አሽከር ሚዜው ደግሞ ከሁሉም በእድሜ አነስተኛ ሲሆን ምግብና መጠጥ ለሙሽራይቱ ማቅረብ ነው የሥራ ድርሻው። ሁለቱ ሚዜዎች ለሙሽራይቱ አባት በሙሽራው አማካይነት እንዲተዋወቁ ሲደረግ የከበቡሽ አባት «ሚዜዎችህ እነማን ናቸው? ስለ ልጄ ኃላፊነቱን የሚወስደው ማነው? አማካሪዋስ? የሚያበረታታትስ ማነው? የሚስጢሯ ተካፋይ ማነው?» የሚሉትን ጥያቄዎች አግተለተሉባቸው። ለዚህ መልስ መልኬ ሁለቱን ሚዜዎች ለከበቡሽ አባት አቅርቦ ካስተዋወቀ በኋላ ሁለቱ ሚዜዎች ወደ መጋረጃው ለመግባት ተፈቅዶላቸው ሙሽራይቱና ሁለቱ ሚዜዎቿ በአንድ ዋንጫ የተቀዳውን ጠላ በመቅመስ ሁሉም እንደ እኅትና ወንድም ለመተያየት ቃል ኪዳን ገቡ።

ከዚያም የሲቪል ጋብቻው ሥነሥርዓት ለአጭር ጊዜ በሙሽራይቱ ወላጆች ቤት ቀጥሎ በሁለቱ ቤተሰቦች መካከል ቀደም ብሎ የተደረገው የቃል ውል እንደገና እንዲታደስ

ተደረገ፡፡ ከበቡሽም በቀጭን ኩታ ፊቷ እንደተሸፈነ ከመልኬ ጋር ባልና ሚስት ለመሆን ቃለ መሐላ ፈፀሙ፡፡

የሥጋዊው ሥነሥርዓት በትልቁ ዳስ ውስጥ በሚደረገው የሠርጉ ድግስ ተጀምሮ ከበቡሽ ለመጀመሪያ ለሕዝብ እስከምትታይበት እስከሚቀጥለው ቀን ቀጠለ፡፡ እስከዚያ ድረስ ግን ከበቡሽን ማንም ሰው እንዲያያት ስለማይፈቀድ በአባቷ ቤት በሚዜዎቿ ተጠብቃ ሲመግቧትና ሲያጫውቷት ዋሉ፡፡ ከዚያም መልኬና እድምተኞቹ ከእንግዶች ጋር ሌሊቱን በሙሉ ሲበሉና ሲጠጡ፣ በአዝማሪው ማሲንቆ እየታጀቡ ዘፈኑንና ቀረርቶውን ሲያቀልጡት አደሩ፡፡

በማግሥቱ እኩለ ቀን ላይ ከሚዜዎቹ አንዱ ከተጋበዙት እንግዶች ለሙሽራውና ለሙሽሪት የምርቃት ገንዘብ መሰብሰብ ጀመረ፡፡ ቀጥሎም ሙሽራይቱ ፊቷ በሻሽ ተሸፍኖ በአንደኛው ሚዜ ታዝላ ከአባቷ ቤት ወጥታ ወደ ዳሱ በመምጣት አዲስ በተነጠፈው ጀንዲ ላይ ከመልኬ ጋር ከተቀመጠች በኋላ ሚዜዎቹ ሁለቱንም ሙሽሮች ማዝናናት ቀጠሉ፡፡ ከዚያም ከበሮው እየተነረተ እያለ ሁለት ሚዜዎች ተነስተው መዝፈን እንደጀመሩ ወዲያውኑ ፉከራውና ሽለላው እየጋለ በመምጣቱ መልኬ ከተቀመጠበት ተነስቶ ግሩም የሆነ የጀግና ፉከራ አሰማ፡፡ የሙሽራይቱ አባት በዚህ በመደሰት ለመታያ ተብሎ ቀደም ብሎ የተሰጣቸውን ገንዘብ ለሙሽራው ሸለሙት፡፡ ምንም እንኳን ወጣቶቹ ወደ ጦር ሜዳ ለመውጣት በአሁኑ ወቅት ዕድሉ ባያጋጥማቸውም ይህ ባህል ከቅድመ አያቶቻቸው ሲወርድ ሲዋረድ የመጣ የጀግንነት ተምሳሌነት ሆኖ ስለሚታይና እንደ ብቁ ሰው አድርጉ ስለሚያስቆጥር ፉከራውና ሽለላው በየሠርጉ ቤት ሲደጋገም ይታያል፡፡

ከሰዓት በኋላ ዘግየት ብሎ (ሚዜዎቹ በቅሎ የያዙ ቢሆንም) ከበቡሽን በጀርባቸው አዝለው አቀበቱን ወጥተው ቁልቁለቱን ወርደው ሸለቆውን በማቋረጥ ወደ መልኬ አባት ቤት ከተፍ አሉ፡፡ አሁንም ቢሆን ከበቡሽን ዓይን (ቡዳ) እንዳይበላት ስለሚፈራ የተሸፈነችበት ሻሽ አልተነሳም ነበር፡፡ እድምተኞቹ እንደደረሱ ወዲያውኑ ሚዜዎቹ ከመልኬ ጋር የቃል ኪዳን ወንድማማቾች መሆናቸውን በማረጋገጥ ቃል በመግባት በአንድ ዋንጫ የተቀዳውን ጠላ ተካፍለው ጠጡ፡፡ በመጨረሻም ሁሉም

ሚዜዎች ሙሽሪትን «እኅቴ» ሙሽራውን ደግሞ «ጓደኛ» ብለው ለመጥራትና በመካከላቸው እንኳን ጠብ ቢነሣ ለማስታረቅ በመስማማት የቃል ኪዳን ጽዋቸውን አነሡ፡፡

# ጉልማሳነትና የትዳር ሕይወት

በጋብቻቸው ጊዜ አንዲት ልጃገረድ ለአካለ መጠን የደረሰች ከሆነ በመሠረቱ መኖር ያለባት ከሙሽራው ጋር በአባቱ ቤት ይሆናል፡፡ በዚህ ሁኔታ የምትገኝ ልጃገረድ ድንግልናዋ በሠርጉ ሌሊት ሊገሠስ ይችል ይሆናል፡፡ በዚህ ጉዳይ ላይ ከበሳል ሚዜዎች አንዱ ሙሽራውን ያማክራል፤ አስፈላጊም ሆኖ ሲገኝ ሙሽራው ድንግል በመውሰድ በሚያደርገው ጥረት ተገቢውን እርዳታ ያደርጋል፡፡ ሙሽራዋም ብትሆን የአካባቢውን ልጃገረዶች በዚህ ሁኔታ የአጋጠማቸውን ልምድ በመጠየቅ ለመረዳት ስለምትችል ለጉዳዩ ብዙም እንግዳ አትሆንም፡፡ ለአቅመ-ሔይዋን ያልደረሰች ልጃገረድ ከሆነች እስከምታድግ ድረስ ክብረ-ንጽህናዋ አይነካም፡፡ ይህን ሁኔታ በመልኬና በከበቡሽ መካከል ከነበረው ግንኙነት ለመረዳት እንችላለን፡፡ ከበቡሽ ለአቅመ-ሔይዋን ያልደረሰች ስለነበረ የምትኖረው ከዘመዶቿ ጋር ነው፣ መልኬም ያው ከእናት አባቱ ቤት ይኖራል፡፡ ከበቡሽ ለሳምንትም ሆነ ለአንድ ወር ወደ አማቶቿ ቤት እየመጣችና እየሄደች ለአቅመ-ሔይዋን እስከምትደርስ ጊዜዋን እያራዘመች ትቆያለች፤ መልኬም ብቻውን የመተኛቱን ኑሮ ይያያዘዋል፡፡

ወጣቷ ሙሽራ አማቷን ወይዘሮ አዳነችን ከመልኬ ወንድሞች ሚስቶች ጋር በመሆን በቤት ሥራ ትረዳለች፤ ወደፊትም በቤቱ ውስጥ ትዳሯን ለመወጣት የሚያስችላትን የወጥ ቤትና የቤት አያያዝ ሥራ በዚህ መልክ ትማራለች፡፡ ቀስ በቀስ አዲሲቱ ሙሽራ ከባለቤቷ የቤተሰብ አባላት ጋር የበለጠ እየተሳሰረችና እየተቀራረበች ትመጣለች፡፡ ከቤተሰብ የመለየቱ ስቀቀን እየቀነሰ ይመጣና በመጨረሻ ቋሚ መኖሪያዋን በባለቤቷ ቤት ታደርጋለች፡፡ ሁሉም ነገር ድንገተኛ አይሆንባትም፤ አካባቢውም አዲስ አይደለም፡፡ በዚህ ዓይነት ከትዳር ጋር የመተዋወቁ ሁኔታ ለሙሽራውም ሆነ ለሙሽሪት እንዲሁም ለሁለቱም ቤተሰቦች ቊንቀትንና ሀሣብን ስለማያስከትል በቤተሰቦች ዘንድ ጥሩ ግንኙነት ይሠፍናል ማለት ነው፡፡

የትንሽ ሴት ልጅ የሙሽርነት ጊዜ የሚደመደመው ሙሽራይቱ እድሜዋ አስራ ሦስት ዓመት አካባቢ ሆኖ ለአቅመ-ሄደዋን እንደደረሰች ድንግልናዋ ሲገሠስ ነው:: ይህም የሚሆነው ሙሽሮቹ ለብቻ ተነጥሎ በሚገኝ በአንድ የሜጉላ ጉጆ ውስጥ በአንድ ላይ ማደር ሲጀምሩ ነው:: ሙሽራይቱ ለአቅመ-ሄደዋን ያልደረሰች ከሆነ በቃል የሚደረገው የጋብቻ ስምምነት ላይ ከመቼ ጀምሮ ከሙሽራው ጋር መተኛት መጀመር እንዳለባት ይገለጻል:: ብዙ ጊዜ የወር አበባ ካዩች በኋላ መሆን እንዳለበት የጋራ ስምምነት እንደሚያስፈልግና ከዚያ በፊት በሚደረግ የግብረ-ሥጋ ግንኙነት በሙሽራይቱ ላይ የአካል ጉዳት ቢደርስ ተጠያቂነትና የገንዘብ ቅጣት ለዘመዶቿ እንደሚወሰን ያስገነዝባል:: የአካል ጉዳቱ ቀላል ከሆነ ግን ጉዳዩ በአብዛኛው ችላ ይባላል:: የአካል ጉዳቱ ከባድ ከሆነ ግን የልጅቷ ዘመዶች ነገሩ ወደ ፍች የሚያዘነብል ሆኖ ከተገኘ ገንዘቡን ለመውሰድ እንዲያስችላቸው በእጃቸው ተይዞ እንዲቆይ ይደረጋል::

እንዲት ሴት የመጀመሪያ እርግዝናዋ በአስራ አምስት ዕድሜዋ አካባቢ ሊከሰት ይችላል:: ነፍስ-ጡር እናት የመውለጃዋ ጊዜ እስከሚቃረብ ድረስ ያው እንደ ድሮው መደበኛ ሥራዋን ስትቀጥል ቆይታ የመጨረሻው ወሯ ሲገባ ቀላል ሥራዎችን ብቻ ስታከናውን ትቆያለች:: በአብዛኛው ጊዜ ኑሮአቸውን በማጠናከር ረገድ እንዲረዳ የመጀመሪያው ልጅ ወንድ ቢሆን ይመረጣል:: ልጁ መጣጉሰ ወይም አካለ ጉደሎ እንኳን ሆኖ ቢወለድ በቅማንቶች ዘንድ ሕይወቱ እንዲጠፋ አይደረግም፡ እንዲሁም ውርጃ የታወቀ ቢሆንም ይቅርታ ሊደረግለት የማይችል ጥፋት ነው:: የጽንስ መከላከያ መውሰድ ባይፈቀድም፣ አንዳንድ ሴቶች ብዙ ጊዜ ውጤት የሌለው ቅጠላ ቅጠል በጥብጠው መጠጣታቸው ግን አልቀረም::

ለብዙ ዓመታት ተጋብተው ከቆዩ በኋላ ወጣት ባልና ሚስቶች ከሙሽራው ወላጆች አጠገብ ቤት ሠርተው ለብቻቸው መኖር ይጀምራሉ:: ደረጃው ከፍ ያለ መሆኑን ለማስገንዘብ በቅማንት ሕብረተሰብ የተለመደውን የእንግዳ ተቀባይነት ባሕርይ በቤታቸው ውስጥ ማንጸባረቅ ይጀምራሉ:: እንደ ቅማንቶች እምነት ማንኛውም ቤት የእግዚአብሔር ቤት በመሆኑ የማይታወቅ እንግዳም ቢሆን ለማንኛውም ቅማንት ክፍት መሆን አለበት:: እንግዳ ሲመጣ ቤት እንዲገባ ይደረጋል፣ ምግብና መጠጥ ከተሰጠ

ው በኋላ ባለቤቱ እግሮቹን ያጥብለታል። የእግር ማጠቡ ጉዳይ በተግባር ላይ ሲታይ ግን ብዙ ሰዎች በዚህ ሁኔታ እግራቸውን እንዲረጥብ አይፈልጉም። ለማኝ የሆኑ ሰዎች ደግሞ ጭብጥ ጥሬ ወይም ቁራሽ እንጀራ ከተሰጣቸው በኋላ ጉዞአቸውን እንዲቀጥሉ ይደረጋሉ። የኢኮኖሚው ሁኔታ ብዙም ስለማያጋድድ ብዙ ደግነትም እንደማያዋጣ ይገነዘባሉ። የተጋበዘ እንግዳ ከሆነ ግን በገፍ ልዩ ምግብና መጠጥ ይቀርብለትና በአፍ በአፉ በማጉረስ ሆዱ ሞልቶ ሊፈነዳ እስከሚደርስ ያጠግቡታል።

## ክቡር የሆነው አዛውንትነት ማዕረግና «ካማ»

የቅማንት ወንድና ሴቶች አብዛኛውን የጉልምስና ዘመናቸውን የሚያሳልፉት የአካባቢው መሬት የምትለግሳቸውን የምርት ውጤት በመጠቀም ኑሮአቸውን በመምራትና ልጆቻቸውን በማሳደግ ነው። ሃምሣ ዓመት ከሞላቸው በኋላ ግን ወደ አዛውንትነት ደረጃ በመሸጋገር የሽማግሌ ሚና መጫወት ይጀምራሉ። በቅማንቶች ዘንድ አዛውንቶች ሕግን በተመለከተ የሚሰጡት አስተያየት ከፍተኛ ግምት ያለው ሲሆን ወጣቶች ስለቤተሰብና ስለእርሻ ጉዳይ እነሱን ማማከር ግዴታ ነው። አዛውንቶችን ማክበርና በጥንቃቄ መያዝ በእግዚአብሔርም ዘንድ ጽድቅን የሚያስገኝ መሆኑን ያምኑበታል።

ቀደም ብሎ ስለ ሕግ ሥነሥርዓት በተመለከትንበት ጊዜ አንድ ሰው ወደ አዛውንትነት ደረጃ ለመሸጋገር «የካማ» ሥነሥርዓተ ቅዳሴ መካሄድ እንዳለበት ተገልጿል። የካማ ሥርዓት በሁሉም ዘንድ ባይሆን በአብዛኛዎቹ አዛውንቶች ከልደትና ከጋብቻ ሥነሥርዓት ባላነሰ ሁኔታ ይከበራል። ለዚህ ደረጃ ብቁ ለመሆን አንድ ሰው ሁለት ፀጉር ማብቀል አለበት፣ ሴቷ ደግሞ የወር አበባዋ መምጣት መቆም (ማረጥ) ይኖርበታል። በዚህ የሽምግልና ሁኔታ የሚገኙ ወንድና ሴቶች ወደፊት ሃጢአት ይሠራሉ ተብለው አይጠረጠሩም። በ«ካማ» ሥርዓተ-ቅዳሴ ያለፈ ሰው ከወር አበባዋ ያልፀዳች ሴት ባለችበት ቦታ አይገኝም፣ ጋብቻ ማፍረስ አይችልም፣ እንዲሁም አረማዊ-አሪታዊ ያልሆነች ሴት የሠራችውን ምግብና መጠጥ መውሰድ ይከለከላል። በዚህ ሁኔታ የሚገኝ አንድ አዛውንት ለእግዚአብሔር የቀረበ ንፁህ ሰው ነው ተብሎ ይገመታል።

የተከበሩ አዛውንት ለመሆን አቶ ረዳ ከካሣው ሥነሥርዓት በፊት «የቁም ተዝካር» ማውጣት ስለነበረባቸው ሁለቱንም ሥነሥርዓቶች በአንድ ቀን ነበር ያካሄዱት። «የቁም ተዝካር» አንድ ሰው ከመሞቱ በፊት የሚደረግ ሥነሥርዓት ሲሆን አንድ ሰው ታማኝና የተከበረ ሆኖ ወደ አምላክ እንዲቀርብ የሚረዳውና ወደ ገነት ለመግባት ጥርጊያውን የሚያስተካክልበት ሥርዓት ነው ተብሎ ይታመናል። የአቶ ረዳ ሥነሥርዓት በተካሄደበት ወቅት የአካባቢው ቄሶች ጸሎት አደረሱ፡ ቤተሰቦቻቸውና ጉረቤቶቻቸውም መርቀዋቸው በሥነሥርዓቱ የነበሩት ሁሉ በአቶ ረዳ ቤት በተዘጋጀው ድግስ መዝናናት ቀጠሉ። አንድ ሰው ድሃ ከሆነ ግን ግብዣው ለቄሶች ብቻ ነው የሚደረገው። (የቄሶች የቁም ተዝካር የሚወጣው ገና በልጅነታቸው ከእግዚአብሔር ጋር ያቀራርባቸዋል ተብሎ ታስቦ ቅስናን በሚቀበሉበት ወቅት ነው።)

በቀጣዩ በተካሄደው የአቶ ረዳ የካሣ ሥነሥርዓት ቀሳውስቱ በእሳቸው ስም ጸሎትና ዝማሬ ካካሄዱ በኋላ አቶ ረዳ በሕይወታቸው ለመጀመሪያ ጊዜ ቅዱሱን ጠላ በሽክና እንዲ ጠጡ ተደርጐ የሥነሥርዓቱ ፍፃሜ ሆነ። ከእንግዲህ አቶ ረዳ ከመሰል አዛውንቶች ጋር በተለያዩ ሥርዓተ-ቅዳሴዎች ላይ ሲገኙ ይህን የተባረከ ጠላ እንደተለመደው ይጠጣሉ ማለት ነው።

## ለቅሶ፣ ለሟች የሚደረግ አሸኛኘት

በቅማንቶች ዘንድ አንድ ሰው ከዚህ ዓለም በሞት ሲለይ ሁለት የሚታሰቡ ሥነሥርዓቶች አሉ። የመጀመሪያው ሟች ከኅብረተሰቡ ተነጥሎ ለዘለአለም ስለሚሄድ በለቅሶና በሙሾ የሚደረግለት አሸኛኘት ሲሆን፡ ሁለተኛው ደግሞ ሰውዬውን ለማስታወስ ነፍሱ ወደ ሌላው ዓለም ስትሄድ ለመሸኘት የሚደረገው የተዝካር ሥነሥርዓት ነው። ለቅሶ የሚለቀሰው ሰውዬው አርፎ ግብዓተ-መሬት ሲፈፀም ሲሆን ሌላው ግን ሟችን ለማስታወስ ተብሎ ከጥቂት ወራት በኋላ የሚደረገውና እንደ ሁለተኛው የቀብር ሥነሥርዓት የሚቆጠረው ተዝካር ተብሎ የሚታወቀው ነው። ቅማንቶች ሞት የሚከሰተው በአደጋ ወይም በበሽታ ምክንያት እንጂ ሞት በእርጅና ምክንያት ይመጣል ብለው አያምኑም። በሽታም ቢሆን በአብዛኛው ልዕለ-ፍጡራዊ በሆኑ ክስተቶች ለምሳሌ እንደዛር፣ ሠይጣን ወይም ክፉ ዓይን (ቡዳ) በመሳሰሉት አማካይነት የሚመጣ መሆኑን ነው

የሚገነዘቡት:: እልፎ አልፎ ማንበብና መጻፍ የሚችል ሰው ከሞተ ከጽሑፉ ቃላት ጋር በተያያዘ መለኮታዊ ኃይል ተቀሰፈ ነው የሚባለው:: ይህ ዓይነት አሟሟት ሆን ተብሎ ወይም እራስን ለማጥፋት የታቀደ ሳይሆን ሰውዬው እራሱ ላይ እንዳመጣው መቅሰፍት ሆኖ ነው የሚቆጠረው::

አንድ ራሱን የገደለ ሰው ሞትን አለቀኑ እንዲመጣ በማድረጉ በቅዱስ ቦታዎች እንዲቀበር አይደረግም፣ የለቅሶና የተዝካር ሥነሥርዓቶችም አይካሄዱለትም:: እራስን በራስ መግደል ማለት ይህችን የተቀደሰች ሕይወት መጥላትና ከተሰጠው ማኅበራዊ ግዴታና ኃላፊነት መሸሽ ስለሆነ ቅማንቶች ከሁሉም የከፋ ፀረ-ማኅበረሰባዊ ድርጊት መሆኑን ያምናሉ:: ሁለቱ ሥነሥርዓቶች ሴቶች በወር አበባ ወቅት ከሞቱም አይካሄድላቸውም:: እንዲት ሴት በወር አበባዋ ጊዜ ከሞተች ቅዱስ ድግናዎችን ታረክሳለች ተብሎ ስለሚገመት ከተባረከው የመቃብር ቦታ ክልል ውጭ ነው አስከሬኗ እንዲያርፍ የሚደረገው::

አንድ ቀን ጥዋት አየሩ ንውሕና ቀዝቃዛ በነበረበት የዘር ወቅት የገበሬው የአቶ ረዳና የቃልቻው የአዮ አባት የሆኑት አቶ አየነው በጠና ታመው በጣር ላይ ሆኑ:: ሕይወታቸው ልታልፍ በሚያጣጥሩበት ወቅት ከበቡሽ አንድ ቄስ እንድትጠራ ተልካ ቄሱ እንደመጡ ጸሎት ካደረሱላቸው በኋላ የመጨረሻውን የኑዛዜ ቃል ተቀበሏቸው:: በዚያው ዕለት ከምሽቱ ላይ በሐዘን የተዋጡት ቤተሰቦቻቸው ከበው ሲያስታምሟቸው ቆይተው የአቶ አየነው ነፍስ ለመጨረሻ ጊዜ አመለጠች:: ወዲያውኑ ለቀብሩ ዝግጅት የአቶ አየነው ሰውነት በሚገባ ታጥቦ በሕይወት እንዳሉ እንዲመስሉ ዓይናቸውና አፋቸው እንዲዘጋ ተደረገ:: ከዚያም አስከሬኑን በጀርባ በማጋደም እጅና እግሩን በአንድ ላይ አሠሩት:: አውራ ጣቶችን አገጣጥመው ካሠሩ በኋላ አስከሬኑን አዲስ በሆነ ነጭ ጨርቅ ሙሉ በሙሉ ገንዘውና ከፍነው በመጨረሻ በስሌን ጠ ቀለሉት:: ወምበሮች በዚህ ዓይነት የሚገነዙና የሚከፈኑ ቢሆንም የእነሱን ለየት የሚያደርገው ነገር ቢኖር አስከሬናቸው ከቅዱስ ድግናው ተቆርጦ በተጠረበና በተገጠመ ሳጥን ውስጥ ሆኖ መቀበሩ ብቻ ነው:: በመሠረቱ አንድ ሰው ጥዋት ከሞተ የቀብሩ ሥነሥርዓት ሳያድር በእዚያኑ ዕለት የሚፈጸም ቢሆንም አቶ

አየነው ያረፉት ከሰዓት በኋላ በመሆኑ ቀብራቸው በማግሥቱ እንዲሆን ተወሰነ::

ሩቅ አካባቢ የሚኖሩ የአቶ አየነው ዘመድ አዝማድና ወዳጆቻቸው ሊሊቱን በመላላክና እንዲሁም ከጋራ ጋራ በሚያስተጋባ የጩኸት ጥሪ የአቶ አየነው መሞት እንዲታወቅና የቀብር ሥነሥርዓቱም በማግሥቱ መሆኑ እንዲሰማ በመደረጉ ከንጋት ጀምሮ ሐዘንተኞቹ ከየአቅጣጫው አቀበቱን በመውጣትና ቁልቁለቱን በመውረድ ሸንተረሮችን አቋርጠው ለክብረ-በዓል የሚለብሷቸውን ነጫጭ ልብሶች አጥልቀው ወደ ሠፈሩ ይጉርፉ ጀመር:: ለቀስተኞች በአቶ ረዳ ቤት ዙሪያ በመሰባሰብ ሐዘናቸውን ሲገልፁ አካባቢው በጠቅላላው በለቅሶ ድምፅ ተሞላ:: የቅርብ የሥጋና የጋብቻ ዘመዶች ደግሞ ሐዘናቸው ከሁሉ በጣም የመረረ ስለነበር ከፊሉ ሙሉ በሙሉ ፀጉራቸውን ሲላጩ ከፊሎቹ መራር ሐዘናቸውን ለመግለጽ ፊታቸውን በእጅ ጥፍሮቻቸው ነጭተው መላለጡት::

ከዚያም የአቶ አየነው አስከሬን በቃሬዛ ላይ ሆኖ በብዙ መቶ በሚቆጠሩ ሐዘንተኞች ታጅቦ የቀብሩ ሥነሥርዓት ወደሚፈፀምበት ቅዱስ ድግና አመራ:: ስልፈኛው ከመቃብሩ ቦታ ላይ እንደደረሰ የሟቹን ቤተሰቦችና ወዳጆቻቸውን ሕዝቡ ከበ እለቅሶው ቀጠለ:: ቤተሰቦቻቸውና ወዳጆቻቸውም የትልቁ አባት የአቶ አየነው የነበሩትን ልብሶችና ቁሳቁሶች በመያዝ «አየነው ቤቱን፣ ቤተሰቡን፣ እንዲሁም በዚህ የነበረውን ደስታ ሁሉ ጥሎ ስለሄደ እንግዲህ በእነዚህ እቃዎች መገልገሉ አከተመ» በማለት ከተሰበሰበው ሕዝብ ጋር ሆነው ዋይታቸውን ይለቁት ጀመር::

ቀጥሎም የአቶ አየነው አስከሬን በተባረከው ድግና ጥልቅ ባልሆነ መቃብር ላይ ተቀመጠ:: አስከሬኑ በቀኝ ጉኑ ተጋድሞ የእግር ጫማ ወደምሥራቅ እንዲያመለክት ነበር የተደረገው:: ይህን ሲያደርጉ ቅማንቶች ወደሚፀልዩበት ወደ ምሥራቅ አቅጣጫ የአስከሬኑ ፊት እንደተቀመጠ አድርገው ነው የሚገምቱት:: የቀብሩን ተግባር ለማጠናቀቅ መጀመሪያ አፈሩ ተመለሰና ከላይ ድንጋይ እንዲቆለል ተደረገ:: አቶ አየነው የካግ ሥነ-ሥርዓት ተደርጉላቸው ስለነበር ቀሳውስቱ ለመዝጊያው ሥርዓተ-ጸሎት ካደረጉ በኋላ መቃብሩን ባርከው ቅጹሉን የጠላ ጠበል

አፈስሱበት። በእነዚህ ሥነ-ሥርዓት ያላለፉ ቢሆን ኖሮ ግን የዚህ ዓይነቱ ሃይማኖታዊ የቀብር ሥርዓት አይደረግላቸውም ነበር።

ከቀብሩ መልስ በኋላ ሰዎቹ ሐዘንተኞችን ለማጽናናትና ራሳቸውም ስለሞት ያላቸውን ፍራቻና ጥርጣሬ ለማለዘብ ለአጭር ጊዜ ቆይታ አድርገው ወደቤታቸው ሲሄዱ ከሩቅ ቦታ የመጡ ዘመድ አዝማዶች ግን እስከ ሦስት ቀን መቆየት ይችሉ ነበር። ከጉረቤት፣ በቅርብ ካሉ የቤተሰብ አባላትና ከማኅበርተኞች በቂ ምግብ ስለሚቀርብ ለሁሉም የሐዘን ተካፋይ ምግብ ማብላት አስቸጋሪ አይደለም።

## ተዝካር፣ ሁለተኛው የቀብር ሥርዓት

የአንድ ግለሰብ ሕልፈተ-ሕይወት የመጨረሻው ሥነ-ሥርዓት የሚጠናቀቀው ሁለተኛው የቀብር ሥነ-ሥርዓት ነው ተብሎ የሚገመተው ከገብዓተ-መሬት ሥነሥርዓት በኋላ ጥቂት ወራት ቆይቶ በባለቤቱ ወይም በልጆቹ ተዝካሩ ሲወጣለት ነው። ይህ ሥነ-ሥርዓት የሚደረገው ሟችን ለማስታወስና ከተቀበረ በኋላም ነፍሱ ወደገነት ገብቷ በደስታ ለመኖር ያስችለዋል ተብሎ ስለሚታመን ነው። ተዝካር ሥረ-መሠረቱ የጥንታዊ አገዎች ሲሆን በቅድመ ክርስቲያን ዘመን ተግባራዊ ያደርጉት እንደነበር ታውቋል። በጥንታዊ አገዎች ምናልባት ሁለተኛው የቀብር ሥነ-ሥርዓት ተብሎ የሚታወቅ ሲሆን ተዝካር የሚወጣው አደገኛ የሆነው የሟች ነፍስ ይህችን ምድራዊ አለም መለኮታዊ ወደ ሆነው ሌላው ዓለም እንዲሄድ ለመሸኘት ነው። ጥንታዊ የሆነው ሥርዓተ-ቅዳሴ በቅማንቶች ተዝካር እስካሁን ያለ በመሆኑ ልዩ የሚያደርገው ቢሆንም፣ በኢትዮጵያ በሚገኙ ኦሪታዊ ፈላሻዎችና በክርስቲያን አማራዎችም ተዝካር ማውጣት ከሃይማኖታዊ ሥነ-ሥርዓቶች አንዱ ነው።

በግምት ሁሉም የቅማንት ኅብረተሰብ የሁለተኛው የቀብር ሥነ-ሥርዓት ላይ ተካፋይ ይሆናል። በሥነሥርዓቱ ላይ ቄሶች የሟች ነፍስ ወደ ገነት እንድትገባ ለእግዚአብሔር ጸሎት ያደርሳሉ። ከዚያም በሥነ-ሥርዓቱ ላይ የተገኘው ሕዝብ የሟች ቤተሰቦች ያዘጋጁትን ድግስ ይበላል፣ ይጠጣል። ኅብረተሰቡ የሟች ነፍስ ወደሌላው ዓለም የሚሸጋገር መሆኑን በማመን «ነፍሱን ምዝግና ይማረው» ይላሉ። ቀሳውስቱና እንግዶቹ

ቤተሰባቸን መርቀው በድጋሚ ግብዣው ይቀጥልና የሥነ ሥርዓቱ ፍፃሜ ይሆናል።

ባለፉት በርካታ ዓመታት ከነበሩት ተዝካሮች ሁሉ በጣም ልቆ የሚገኘው እ.ኤ.አ. የካቲት 1965 ዓ.ም. ተደርጐ የነበረው የአሁኑ ወምበር ሙሉነህ አባት የነበሩት የወምበር መርሻ ዘውዱ ተዝካር ነበር። እ.ኤ.አ. በኅዳር ወር 1964 ዓ.ም. የሞቱት ወምበር መርሻ ዘውዱ የዑዱልጋ ወምበር በ1941 ዓ.ም. ሲሞቱ በወምበርነት ተተክተው ሲያገለግሉ መቆየታቸው ታውቋል። ሥነ-ሥርዓቱ በሁለት ተከፍሎ በመጀመሪያ ለክርስቲያን ቅማንቶች ሁለተኛው ደግሞ ለአረማዊ-አሪታዊ ቅማንቶች ነበር የተደረገው። ያንን በቅማንት አገር ታይቶ የማይታወቀውን ታላቅ ተዝካር ከዚህ ቀጥሎ እንመለከተዋለን።

የመጀመሪያው ሥነ-ሥርዓት ክፍል ዕሑድ የሚጀምር ስለነበር በዓሉን ለማክበር በብዙ መቶ የሚቆጠሩ ክርስቲያን ቅማንቶች ጃልሸቭ በሚገኘው በወምበሩ መኖሪያ ሠፈር ተሰበሰቡ። የተሰበሰበው ሕዝብ ብዛት በአንድ ትልቅ የገበያ ቀን ከሚውለው ሕዝብ የሚያንስ አልነበረም። ስድስት በሬዎች ነበር ለድግሱ የታረዱት። በድግሱ ላይ የተሰበሰቡት ክርስቲያን ቅማንቶች በየጊዜው በአንድ ላይ «የመርሻን ነፍስ ምዝግና ይማር!» እያሉ ይጮሁ ነበር።

ለክርስቲያኖች ዕሑድ የተጀመረው ግብዣ ሰኞ ዕለት እንዳበቃ ረቡዕ ምሽት ላይ ደግሞ አረማዊ-አሪታዊ ቅማንቶች ብቻ የሚካፈሉበት ድግስ ተጀመረ። ስምንት ያህል ቄሶችና ስማንያ ሌሎች ሰዎች ነበር የተገኙት። አንዳንዶቹ በዚህ በዓል ለመገኘት ለአንድ ቀን በእግራቸው ተጉዘዋል። ወምበሩ፣ ቀሳውስቱና በካማ ሥነ-ሥርዓት ያለፉ አዛውንቶች በተለይ ለዚህ በዓል ተብሎ በጨፈቃ በተሠራው ጐጆ ውስጥ በአንድ ላይ ሲሰበሰቡ ሌሎቹ ተራ ሰዎች ውጭ ሆነው ይጠባበቁ ነበር። ከቀሳውስቱ ጸሎትና ቅዳሴ በኋላ ግብዣው ቀጠለ። በጐጆው ውስጥ ላሉት ምግባቸው በተለይ የሚዘጋጀው ከደጃፍ ላይ ነበር። ከጐጆው መሐል ላይ የተባረከው ጠላ የተሞላባቸው ሸክናዎች ተራ ሰዎች እንዳያዩዋቸው በትንሽ መጋረጃ ቢጤ ተከልለው ተደርድረዋል። የተባረከውን ጠላ በተለይ በጠባቂነት የተመደበው ሰው በጐጆው ለታደሙት እንግዶች ያድል ነበር።

በማግሥቱ ከጠዋቱ ሁለት ሰዓት ጀምሮ ሁለተኛው የሥነ-ሥርዓቱ ክፍል ቀጠለ። ከአራት ማኅበረሰቦች (ደብር) የተውጣጡ ስምንት ቄሶች በወምበሩ እየተመሩ ሥርዓተ-



በጭሊጋው ወምበር አባት ተገቦር ሕዝቡ በግብግብ ላይ እንዳለ።

ጸሎትና መዝሙር አሰሙ። በጸሎቱ ላይ ስለቅማንት ጎብረተሰቦች ደኅንነት፣ ስለሟች ነፍስ የምዝማኗን፣ የክብርዋንና የጵላተ-ሙሴን ስም በማንሣት ጸሎት ያደርጉ ነበር። ጸሎቱ እንዳበቃ ፊታቸውን ወደ ምሥራቅ በማዞርና እጃቸውን በማንሳት ወደታች ዝቅ ብለው በመውረድ መሬቱን ሳሙ። ከዚያም በዚያው አጠገብ በሚገኝ አንድ የመስዋዕት ማቅረቢያ ቦታ ለከፍተኛው ቄስ አንድ የሚያገጣ በሬና ሦስት በጐች ቀርበውለት አነስተኛ ቄሶች የእንስሶችን እግሮች ጠፍረው እየያዙለት አረዳቸው። ድግሱ ቀኑን ሙሉ ውሎ እስከ ማግስቱ እኩለ ቀን በቆየበት ጊዜ 200 ጋሎን ጠላና 20 ጋሎን ጠጅ ተጠጣ፤ በብዙ መቶዎች የሚቆጠሩ እንጀራዎች በሥጋ ወጥ ተበልተው አለቁ።

ምሽት ላይ አነስተኛ የወረባ ሥነ-ሥርዓት ነበር። ወረባው ዘአንድ ቄስ እየተመራ ቄሶቹ ልዩ የሆነውን ዝማሬያቸውን ያሰሙ ነበር። ሁለት ቄሶች በሦስት ሜትር ተራርቀው በቀስታ እንቅስቃሴ ዙሪያውን በመሽከርከር መዘመር ቀጠሉ። ቄሶቹ እየደጋገሙ የአንዷን የተከበረች አሮጊት ስም በዜማ ሲያነሡ ሴትዮዋ ተነስታ በዘፈኑ ተቀላቀለቻቸው። ከዚያም ሌሎች አሮጊት ሴቶች ተራ በተራ እየዘፈኑ ሲጨርሱ ፊታቸውን በመጋረጃ ወደተጋረደው የተባረከ ጠበል አዙረው እጅ በመንሳት ይቀመጡ ነበር። ሥነ-ሥርዓቱ ሲያልቅ የተባረከው ጠጅ ታደለ። ሌላው ሕዝብና ቀሳውስቱ ሌሊቱን በሙሉ እየወጉ ሲበሉና ሲጠጡ አድረው ተጨማሪ ሌላ ሥነ-ሥርዓት ባይኖርም በማግሥቱ የመዝናናቱ ጉዳይ ቀጠለ። በመጨረሻም የመስነባበቻ ምልክት መስጫ የሆነው በጋኖች ውስጥ የነበረው አተላ ሲደፋ ሕዝቡ ጃልሻሉን በመልቀቅ ከሰዓት በኋላና በምሽት ወደየቀየው ተመለሰ።

ቄሶች የግለሰቦችን ሁለተኛውን የሙት ዓመት ለማስታወስ በተጨማሪ «ዓመታት» ተብሎ የሚታወቀውን የቅዳሴ ሥነሥርዓትም ያካሂዳሉ። ይህ ሁኔታ በየዓመቱ የሟች አስከሬን ባረፈበት ድግና ለብዙ አሥርተ ዓመታት የሚቀጥል ይሆናል። የእግዚአብሔርን ትዕዛዛትና የቅማንትን ሥነምግባር ሕግጋት ጠ ብቀው ሕይወታቸውን ያለፉትን ትውልዶች ለማስታወስ የሚደረግ ሥነ-ሥርዓት መሆኑን እንገነዘባለን።

# ምዕራፍ አሥር

## ባህላዊ ለውጥና ቅማንት

የመጨረሻ በሆነው በዚህ ርዕስ የቅማንት ሃይማኖትና ከዚሁ ጋር የተሳሰረውና ተነጥሎ ሊታይ የማይችለው የባህል ድንበር መቆጣጠሪያ ስልታቸው በአማራው ባህል ውሕደት (አምሃራይዜሽን) ሂደት የተጫወቱትን ሚና እንዳስሳለን:: የቅማንት ኅብረተሰብ የድንበር መቆጣጠሪያ ስልት የአካባቢው ማኅበራዊ-ባህላዊ ነፀብራቅና ውርስ ባሕርይ ነው ሊባል ይችላል:: በመሆኑም ምንም እንኳን ቅማንቶች የበላይነት በነበረው በአማራው ሕዝብ ተከበው የኖሩ ቢሆንም፣ ቴክኖሎጂና መለኮታዊ እምነቶች ለሕይወት አስፈላጊ የሆኑትን ነገሮች ከማግኘትና ተለዋዋጭና አስተማማኝ ካልሆነው መልክአ-ምድራዊ ተዕፅኖዎች ከሚመነጩ ሥጋቶች ጠብቀዋቸው እንዲቆዩአቸው ሁሉ ይህ ባህላዊ ውርስም ሁሉን ዓይነት ችግሮች ተቋቁሞ ባህላቸው ሳይበረዝ ማንነታቸው ተጠብቆ እንዲቆይ ረድቷቸው ነበር:: ሆኖም በመጨረሻ የአማራን ባህል መቀበል ግዴታ እየሆነ በመምጣቱ የቅማንት ማኅበረሰብና ባህሉ እየቀረ መጥቷል::

ለውጥን ሲከላከል የነበረው የባሕል ድንበር አጥር እያላቸው ለምን የቅማንትነት መለያቸውና የኑሮ ዘይቤአቸው በከፍተኛ ፍጥነት እየተለወጠ እንደመጣ እንመረምራለን:: እዚህ ላይ በተጨማሪ መነሣት የሚገባው ነገር ቢኖር የቅማንት ባህላዊ ለውጥ ለምን የምዕራባዊያንን (የፈረንጆችን) ፈለግ እንዳልተከተለና በመጨረሻም የአማራው ባህል በቅማንቱ ላይ ብቻ ሳይሆን በአጠቃላይ በሌሎች የኢትዮጵያ ሕዝቦችም ላይ የአስከተለውን ተፅዕኖ እናያለን::

የቅማንት የአማራን ባህል በመቀበል በባህል ለውጥ ወደ አማራነት የመለወጡ (አምሃራይዜሽን) ሂደት በሦስት ደረጃዎች ተከፍሎ ሊታይ ይችላል:: የመጀመሪያው፣ ከፍተኛውና የመጨረሻው በማለት ተለይተዋል:: የአማራን ባህል የመቀበል ሂደት በዝርዝር ከመታየቱ በፊት ስለሂደቱ አጭር የሆነ አጠቃላይ መግለጫ መስጠት አስፈላጊ ይሆናል:: የመጀመሪያው የአማራ ባህል በሌሎች ሕዝቦች ላይ ለዘብ ባለ መልኩ ተቀባይነት ማግኘት

የጀመረው አማራው የኢትዮጵያን የመንግሥት ሥልጣን እ.ኤ.አ ከ1270 ዓ.ም. ጀምሮ ሲረከብ ነበር። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ቅማንቶች ከአማራው ጋር ቀጥታ ግንኙነት የነበራቸው ቢሆንም የራሳቸው የሆነውን ማኅበራዊ መታወቂያቸውን ይዘው በመንዛቸው የአማራን ባህል የመቀበሉ ሁኔታ ዘገምተኛ ነበር።

የአማራን ባህል የመቀበሉ ሂደት በዝቅተኛና በአዝጋሚ ደረጃ ላይ የነበረ ቢሆንም፣ አፄ ዮሐንስ አራተኛ የተለያዩ ብሔረሰቦችን በአንድ ላይ አሰባስቦ አንድ ጠንካራ የኢትዮጵያ መንግሥት ለማቋቋምና ከውጭ የሚመጣን ጠላት በጦር ሃይል ለመመከት እንዲረዳቸው አስበው በማስገደድ ክርስቲያን እንዲሆኑ የማድረጉን ፕሮግራም ሲያወጡ አዝጋሚነቱ ቀርቶ ሂደቱ ተፋጠነ። ስለሆነም ቅማንት የክርስትናን ሃይማኖትን ተቀብሎ አማራ የማድረጉ ሂደት ከፍተኛው እመርታ ላይ ደረሰ። ንጉሠ ነገሥቱ ለዘመናት የቆየውን አረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖት ተጠብቆ እንዲቆይ ያደረገውን የማኅበራዊ ድንበር አጥር በማያዳግም ሁኔታ እንዳልነበረ በማድረጋቸው በቅማንት ላይ የደረሰው ባህላዊ ለውጥ በኢትዮጵያ ካሉት ብሄረሰቦች ላይ ከተደረገው ተፅዕኖ ሁሉ የከበደ ነበር።

ከሁለተኛው የዓለም ጦርነት በኋላም በግዴታ አማራ የማድረጉ ሁኔታ እንደገና አገርሽቶ በቅማንት ማኅበራዊና ባህላዊ ሥርዓት ላይ የተፅዕኖ እርምጃ በመውሰዱ የአማራን ባህል እንዲቀበሉና በባሕል ለውጥ አማራ እንዲሆኑ የመጨረሻው የእንቅስቃሴ ክፍል ነው እንላለን።

## የመጀመሪያው ወደአማራነት የመለወጥ ሂደትና ሕብረ-ብሔራዊ መቻቻል

በአማራው ሕዝብ የተከበቡት የቅማንትና የሌሎች አገው አካባቢዎች ከአማራው ባሕል ጋር መተዋወቅ የጀመሩት ገና «የመጀመሪያው አማራ» (ፕሮቶ-አምሃራ) እ.ኤ.አ. በ1000 ዓ.ም. አካባቢ የተከዜን ወንዝ ተሻግሮ በስተደቡብ ካለው የአገው ሕዝቦች ጋር ግንኙነት ሲፈጥር ነበር። ቀደም ብሎ በምዕራፍ ሁለት እንደተገነዘብነው የአማራው ሕዝብ ባህል እየተጠናከረና የአገው ሕዝብ ብዛት እየቀነሰ በመምጣቱ ሁኔታው አስቀድሞ እንደነበረው የባህል መቀላቀል (መዳቀል) መሆኑ ቀርቶ ቀስ በቀስ የአማራው

ባህል የሌሎችን ባህል እየዋጠ ጠቅላላ የባህል ውሕደት እየሆነ መጣ። «አማራ የመሆን ሂደት» (አምሃራይዜሽን) እያልን የምንጠራው የባሕል ውሕደት በሌሎች በርካታ አገዎች ዘንድ በ15ኛው ክፍለ ዘመን መገባደጃ ላይ ነበር የተጠናቀቀው።

በተወሰኑ አንዳንድ አካባቢዎች በባህል ለውጥ አማራ የማድረጉ እንቅስቃሴ ዘገምተኛ ስለነበር አንዳንድ የአገው ጉጣዎች አማራ በሆነው ሕዝብ ተከበው ልዩ የሆነውን ባህላቸውን በአካባቢያቸው ጠብቀው ለመኖር ችለዋል። በዚህ ሁኔታ አገዎችና ጉረቤቶቻቸው የሆነው አማራው በአካባቢያቸው የተረጋጋና መቻቻል የሰፈነበት ሕብረ-ማኅበረሰብ ፈጥረው መኖር ቀጠሉ። የባህል ውሕደቱ ሂደት ፍጥነት አንዱ ከሌላው የተለየበት ልዩ ልዩ ምክንያቶች ነበሩ። የስሜንና የላስታን ሁኔታ የተመለከትን እንደሆነ አካባቢዎቹ ተራራማና ጉራንጉር ስለሚበዛባቸው የአማራን ባህል በማስራጨቱ ረገድ ከፍተኛ ተፅዕኖ ነበረው። በቋራ አካባቢ የሚገኙት አገዎች ደግሞ ከአማራው የሥልጣን ማዕከል እርቀው ይኖሩ ስለነበር ባህላቸውን እንደያዙ ለረዥም ጊዜ ለመቆየት ችለዋል። በሌላ በኩል ለምሳሌ በስሜን፣ በላስታ፣ በአገው ምድር የሚገኙ አገዎች በመልክአ-ምድሩ በመጠቀም አብዛኛውን ጊዜ በጦር ሃይል በመቋቋም ለዘመናት ባህላቸው በአማራው ባህል የመለወጡን ሂዳት ገትተውት ቆይተዋል።

የአገው ሕዝብ በሰፊው በውሕደት አማራ የመሆኑን ሂደት ከመያያዙ በፊት የቅማንቶች አረማዊ-ኦሪታዊ የሆነው ሃይማኖታቸው በአነስ መልኩ አረማዊ በበለጠ መልኩ ደግሞ ኦሪታዊ ከሆኑት በጠላትነት ከሚተያዩት ሌሎች አገዎች ልዩ ያደርጋቸው ስለነበር ቅማንቶት የራሳቸው የሆነውን የመቆጣጠሪያ ስልት በመቀየስ ይበልጥ ኦሪታዊ በሆነው ባህል ሳይዋጡ ቆይተዋል። ይህ ባይሆን ኖሮ ተመሳሳይ ሕዝብ እንደመሆናቸው፣ አካባቢያቸውም ኩታ-ገጠም እንደመሆኑና ሌሎች አገዎችም በሕዝብ ብዛት ስለሚበልጡ የባህሉ ውሕደት ቀላል በሆነ ነበር። ከዚህም በስተቀር በተመሳሳይ ሁኔታ የባህል መዳቀል (መቀላቀል) መቆጣጠሪያ ስልታቸው እያደገና እየዳበረ በመምጣቱ ዙሪያውን ከቦአቸው የነበረውን የአማራውን የባሕል ተፅዕኖ ፈጣን እንቅስቅሴ ለመግታት አስችሏቸዋል። በመሆኑም የአማራውና የቅማንቱ ባህሎች በመቻቻል የተረጋጋ ኅብረ-ማኅበረሰብ መቻቻል ሠፍኖ

እንዲቆዩ በመርዳቱ ቅማንቶች ባህላዊ ሕልውናቸውን ከሌሎች የአገው ጐሣዎች በተለየ መልክ ጠብቀው ለመኖር በቅተዋል።

ምንም እንኳን አገዎች በየጊዜው ከፍተኛ ተቃውሞ ቢያሳዩም፡ እንዲሁም ወደኋላ የሚጐትቱ የተለያዩ ምክንያቶች ቢያጋጥሙም ፈረንጆች (አውሮጳውያን) ወደ ኢትዮጵያ ከመምጣታቸው እ.ኤ.አ. ከ1500 ዓ.ም. በፊት በነበሩት ምዕተ ዓመታት በባህል ለውጥ ወደ አማራነት የመለወጣቸው ሂደት በጣም በሰፊው ቀጥሎ ነበር። የቅማንት ሕዝብ በአማራው የፖለቲካ አገዛዝ ሥር መቼ እንደወደቀ በትክክል ባይታወቅም ምናልባት በቅማንቶች መሬት (አገር) ላይ የተቆረቆረችውና እራሳቸውም በማንኛውም ረገድ ይደግፏት የነበረችው የአማራው መንግሥት ቋሚ መናገሻ ከተማ የነበረችው ጐንደር በ1600ዎቹ ዓ.ም. ስትመሠረት በመጀመሪያዎቹ ዓመታት ሳይሆን አይቀርም። ቅማንቶች ነበሩ በሰው ኃይል፣ በእርሻ ውጤቶችና በማገዶ ረገድ የጐንደር ከተማን ቀጥ አድርገው ይዘዋት የነበረው። በተለይ ማገዶ አቅራቢ በጐንደር ከተማ አካባቢ ባይኖር ኖሮ ሌሎች የኢትዮጵያ ከተሞች እየተመሠረቱ እንደጠፉት ሁሉ የጐንደርም ዕጣ ፋንታ ይኸው ነበር የሚሆነው።

እንደ አብዛኛዎቹ የአገው ጐሣዎች ቅማንቶች ብዙም አማራውን በኃይል ለመቋቋም ባለመሞከራቸው በሠላም እንዲኖሩ ተትተው ነበር። የቅማንቶችን አፈ-ታሪኮችና የአማራውን መዋዕለ ዜናዎች ስንመረምር በሁለቱ ሕዝቦች መካከል ምንም ዓይነት ግጭት እንዳልነበረ፡ ነገር ግን በአማራውና በሌሎች አገዎች መካከል ጦርነቶች እንደተካሄዱ ይገልጻሉ። ቅማንቶች በሠላም መኖርን መርጠው ግብር ብቻ እየገበሩ አርፈው በመቀመጣቸው አማራው የአገዛዙን ሥርዓት በመዘርጋት የቅማንቱን ፖለቲካዊና ሃይማኖታዊ ሥርዓት መደምሰስ አስፈላጊ ሆኖ አላገኘውም።

ቅማንቶች በአማራው ሥር በሠላም መኖርን የመረጡበትን ምክንያት ስንመረምረው በአካባቢያቸው የቅማንት ጠላት ናቸው ብለው የፈረጇአቸው በአብዛኛው አረማዊ የሆኑ አገዎች እንዳይተናኮሉአቸው አማራውን አጋር ለማድረግ ታስቦ እንደሆነ ከአፈ-ታሪካቸው እንገነዘባለን። ከዚህም በስተቀር ቅማንቶች እንደ ሌሎች አገዎች አክራሪ አረማውያን ባለመሆናቸውና ሠላማዊ ሆነው በመገኘታቸው በአማራው ከመደምሰስ ተርፈዋል። በአጭሩ

ወታደራዊ ኃይል፣ ማኅበራዊ አደረጃጀትና ቴክኖሎጂ እንደ ፈላሻ የመሳሰሉትን የአገው ቅርንጫፎችን ሕልውና አስከብሮ ሊያቆያቸው ባለመቻሉ በአማራው ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ በጦርነት ተደምስሰው በአሁኑ ጊዜ በሰሜን ማዕከላዊ ኢትዮጵያ ተበታትነው እንዲኖሩ ሲገደዱ ቅማንቶች ሠላምን የመምረጡ ሁኔታ ካላቸው ከፍተኛ ሃይማኖታዊ ሥነምግባር ጋር ተዳምሮ የጐሣው ሕልውና በሚገባ ተጠብቆ እንዲቆይ ረድቷል።

በማኅበራዊና በፖለቲካ አደረጃጀት ረገድ በአማራው ባላባታዊ አገዛዝ ሥርዓት ሥር ሆነው ከፊል የራስ-ገዝነት መብት የነበራቸው ከመሆኑም በላይ በባህላዊ ሥነሥርዓት በኩል ሙሉ በሙሉ ነፃ በመሆናቸው አስፈላጊ ያልሆነ የተለየ ባህል ወደራሳቸው ማኅበራዊና ባህላዊ ሥርዓት ሠርጐ እንዳይገባ ለመከላከል አስችሏቸው ነበር። እዚህ ላይ መገንዘብ የሚያስፈልገን የቅማንቱ ኅብረተሰብ ከአማራው ጋር በበጐ ፈቃደኛነት የፖለቲካና የኤኮኖሚ ግንኙነት ባይመሠረት ኖሮ ቀደም ብሎ የአማራን ባህል በግድ የመቀበሉ ሁኔታ የማይቀር እንደነበር ነው።

በፍላጐት ተቀባይነት ካገኙት የአማራ ባህል መካከል ቴክኖሎጂ ነክ ነበሩ። እንደሚታወቀው ሁሉ በያዝነው ሁለተኛው ሺ ዘመን ቀደም ብሎ በነበሩት ክፍለ ዘመናት ጥንታዊ የሆነውን የራሳቸው የነበረውን የጓሮ አታክልት እርሻ አስተራረስ ዘዴ በመተው የአማራውን የተሻለ የእርሻ ዘዴ መውረሳቸው ይታወቃል። የሕብረ- ማኅበረሰቦች ተረጋግቶ መኖር ውሕደትን ለጊዜው የሚገታ እንጂ ጨርሶ በሩን መዝጋት ስላልሆነ የቅማንት የባህል ድንበር የመቆጣጠሪያ ስልቶችን እያለፉ ቴክኖሎጂ-ነክ ያልሆኑ አንዳንድ የአማራ ባህሎችም በቅማንቶች ዘንድ ተቀባይነት ሳያገኙ አልቀሩም። ይህም በመሆኑ አንዳንድ በክርስትና ሃይማኖት ውስጥ ያሉ መሠረታዊ ሰምነቶችን ወይም ባህሎችን ወደራሳቸው ወስደው ሲጠቀሙባቸው ቆይተዋል። ለምሳሌ በ19ኛው ክፍለ ዘመን አጋማሽ ላይ የቅማንት የግል መጠሪያ ስሞችን በመተው የአማራ መጠሪያ ስሞችን መጠቀም ጀምረዋል።

ለረዥም ጊዜ በቆየው የመጀመሪያው የአማራ ባህል የመቀበሉ ሂደት በፈጣን የባህል ውሕደት እንዲተካ ለማድረግ ያስችል የነበረው ብቸኛ አማራጭ የቅማንቱን ሃይማኖትና አብረው የተሳሰሩትን የባህል ድንበር መቆጣጠሪያ ስልቶችን በማስወገድ

ይሆን ነበር። እንዲሁም በአማራውና በቅማንቱ የአካባቢ ማኅበራዊና ባህላዊ የመቻቻል ግንኙነት ምክንያት በማዝገም ይካሄድ የነበረው ውሕደትም በዚሁ መልክ ለብዙ ዘመናት ሊቀጥል በቻለ ነበር። ሆኖም አዲስ የሆኑ ለውጥ ማስከተል የሚችሉ የውጭ ሁኔታዎች በመካከሉ ስለተከሰቱ ሊሆን አልቻለም።

## ከፍተኛው የባህል ለውጥ ሂደትና የማኅበራዊ ድንበር የመቆጣጠሪያ ስልቶች መፈረካከስ

የመጀመሪያው የቅማንት የአማራን ባህል ተቀብሎ በውሕደት አማራ የማድረጉ እንቅስቃሴ ከቅማንቶች መካከል ቅርብና ታማኝ የሆኑ ባለሟል በነበሯቸው በአፄ ቴዎድሮስ 2ኛ ዘመነ መንግሥት (እ.ኤ.አ. ከ1855 እስከ 1868) ቀጥሎ ነበር። አሁንም ቢሆን ቅማንቶች አፄ ቴዎድሮስን ብዙ ጊዜ እንደረዷቸውና በአፀፋውም አፄው ብዙ ደግና በጐ ነገሮችን እንዳደረጉላቸው የሚናገሩት በርካታ ታሪኮች አሏቸው። ከእሳቸው ቀጥሎ ግን የክርስቲያን አክራሪ መሪ የነበሩት አፄ ዮሐንስ አራተኛ የቅማንትን ሃይማኖታዊ ሥርዓት በከፊል በማፈራረስ ቅማንቱ ሙሉ በሙሉ የአማራን ባህል እንዲቀበል የማኅበራዊና የባህላዊ በሩን ከፈቱት።

በአፄ ዮሐንስ አራተኛ ዘመነ መንግሥት የኢትዮጵያ ነፃነት በግብፆች፣ በሱዳን ማኅዲስቶችና (ድርቡሾች) በአውሮጳ ቅኝ ገዥዎች በተለይም በጣሊያን ወረራ ምክንያት አደጋ ላይ ሊወድቅ ተቃርቦ ነበር። ከበባ ሲያደርጉ የነበሩት ኃይሎች ሕዝቡን በመከፋፈል የእስልምና ሃይማኖት ያላቸውን ኢትዮጵያውያን ድጋፍ ለማግኘት የሚያደርጉትን ጥረት ለማክሸፍ አፄ ዮሐንስ በተለያዩ ሃይማኖት የተከፋፈሉትን ኢትዮጵያውያን አንድ አድርጉ ለመግዛት ተነሣሡ። ሠራዊታቸውን ዘመናዊ የጦር መሣሪያ በማስታጠቅ እስላሞች፣ አረማዊ-አሬታዊ ቅማንቶች፣ አሬታዊ ፈላሻዎችንና የሙስሊም-አረማዊ ወይጦዎችን በአዋጅና በኃይል የክርስትናን ሃይማኖት እንዲከተሉ ማስገደዱን ተያያዙት።

አስገድዶ የማጥመቁ ተግባር በቅማንቶች ላይ ውጤታማ በመሆኑ የአማራውን ባህል የመቀበሉ ሂደት ከፍተኛ ደረጃ ላይ ደርሶ ነበር። እስላሞችና ፈላሻዎች በዚያን ጊዜ በጣም ብዛት

የነበራቸውና በተለያዩ አካባቢዎች ይኖሩ ስለነበር ተፅዕኖው ይህን ያህል ከባድ አልነበረም። ቅማንቶች ግን ቁጥራቸው አነስተኛና በአንድ አካባቢ ተሰብስበው ይኖሩ ስለነበር፣ የአማራው ማዕከል ከሆነችውም የጐንደር ከተማ አጠገብ በመሆናቸውና የመሬት ባለመብትም ስለነበሩ በአማራው በኩል በቀላሉ ጥቃት ሊሰነዘርባቸው እንደሚችል ለመገመት አያዳግትም። የፈሩት አልቀረም። አንዳንዶቹ ቅማንቶች በመግሪያ በመገደዳቸው ከፊሎቹ ደግሞ መሬታቸውን ሊነጠቁ በመሆኑ በክርስትያንነት ተጠምቆ የአማራን ባህል ከመቀበል በስተቀር ሌላ አማራጭ አልነበራቸውም። አፄ ዮሐንስም የክርስትና ሃይማኖትን የተቀበሉትን ከግብር ነፃ በማድረግ ያበረታቷቸው ነበር። በሌላ በኩል ደግሞ የሃይማኖት ለውጡን ለማመቻቸት በከርከር የሚገኘውን የቅማንቶች ሃይማኖታዊ መሪ ማዕከል በማስነሣትና ድሮ ወምበሩ የነበረውን ግብር የመሰብሰብ ሥልጣን በመግፈፍ ግብር ሰብሳባው በባላባታዊው አገዛዝ የመሬት ሥሪት እንዲወድቅ አደረጉት። ይህ በመሬት ሳቢያ እያስፈራሩ ክርስትናን የማስፋፋቱ ጉዳይ በቅማንቶች ላይ ተግባራዊ ቢሆንም ሥረ-መሠረት በሌላቸው ፈላሻዎች፣ አዳኝ ወይጦዎችና እስላሞች ሁሉም መሬት አልባ ስለነበሩ በሚገባ ተግባራዊ አልሆነም።

ከዚያም ደርቡሾች አፄ ዮሐንስን በ1887 ዓ.ም. ገድለው በቅማንት አካባቢና በጐንደር የሚገኙትን አብያተ-ክርስቲያናት በማቃጠላቸውና በማፈራረሳቸው ቅማንትን ወደ ክርስትና ሃይማኖት የመለወጡ ሂደት እየቀዘቀዘ መጣ። በዚያን ጊዜ ብዙ ቅማንቶች ወደነበሩበት እምነት ቢመለሱም በርካታ በከርከር የሚገኙ ቅማንቶች መሬታቸው በጉልበት ተይዞ የጭሰኛ ግብር እንዳይጣልባቸው ክርስቲያን ሆነው መቆየትን መረጡ።

ወደክርስቲያንነት በመለወጣቸው ምክንያት የቀድሞው ሥርዓት በመፈራረሱ በምሥራቅ ይገኙ የነበሩ ቅማንቶች ለከርከር ወምበር ይገብሩ የነበረው ግብር ተቋረጠ። በጭልጋ የነበሩ ቅማንቶች ግን የክርስትና ሃይማኖትን እንዲቀበሉ ብዙም የኃይል አስገዳጅ ሁኔታ ስላላጋጠማቸው እ.ኤ.አ. እስከ 1930 ዓ.ም. ድረስ ለወምበሩ ሲገብሩ ቆይተዋል።

የተጠመቁ ቅማንቶች ወደ ገነት እንዳይገቡ ወምበሩ ለምን አላወገዘም ተብሎ መጠየቁ አይቀርም። ሁለት ምክንያቶች ነበሩ።

አንደኛው ምክንያት ጥንታዊ ወምበሮች እንደጠቆሙት የተጠመቁ ሰዎች ከባድ መቅሰፍት እንደሚደርስባቸው በአፈ-ታሪካቸው አስቀድሞ የተነገረ በመሆኑ ሲሆን በሁኔታው የተደናገጡ ገበ-ሬዎችም ይህን ሁኔታ ለአማራው የክርስቲያን ሹም ሲገልፁ ደግሞ ሹሙ በአረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖት ተከታዮችና ይህን እርግማን በተናገሩት ላይ እርግጠኛ የሆነ መቅሰፍት እንደሚደርስ በመስበኩ ግራ በመጋባታቸው ሲሆን፣ ሁለተኛው ምክንያት ደግሞ የእነሱ ምዝግና እና የክርስቲያን እግዚአብሔር አንድ መሆናቸውን ቀስ በቀስ በማመናቸው ነበር:: ሌሎች የቅማንት መላእክት ከሌሎች የክርስቲያን ቅዱሳን ጋር ተመሳሳይነታቸውን መቀበሉም ለዕምነት ለውጡ አስተዋፅኦ አድርጓል::ከሁሉም በላይ ደግሞ የቅማንትንም ሆነ የክርስቲያን ሃይማኖትን ቢከተሉ ሁለቱም መንገዶች ጥሩ ወደሆነችው ሰማያዊ ገነት መንገድ የሚያመራ መሆኑን በመቀበላቸው ነበር::

አስገድዶ የባህል ለውጥን እንዲቀበሉ የማድረጉ ጉዳይ የቅማንትን ሃይማኖታዊ ድርጅት ጨርሶ ባያጠፋውም እንደ መሠረት ድንጋይ የጠነከረውን የባህል የድንበር አጥር ግን በሚገባ በማነቃነቅ እንገዳግዶት ነበር:: ምንም እንኳን ከአረማዊ- አሪታዊው ሃይማኖት እስኪል ውጭ ቢሆኑም ክርስቲያን የሆኑት ቅማንቶች ቁጥር በርካታ ስለነበር በሥጋ ዝምድና እና በማኅበር ቃል-ኪዳን እንደተሳሰሩ ነበር:: አረማዊ-አሪታዊ የሆኑ ቅማንቶችም ክርስቲያን ከሆኑ የሥጋ ዘመዶቻቸው ጋር የቅርብ ዕለታዊ ግንኙነት ስለነበራቸው ይህም ሁኔታ ከውጭው የክርስቲያን ዓለም ጋር ባለው ግንኙነት እንደ ድልድይ ሆኖ ያገለግል ጀመር:: ወደ ክርስቲያን የመለወጡ ሂደት የአረማዊ- አሪታዊውን የቅማንት ኅብረተሰብ ማኅበራዊና ኤኮኖሚያዊ ተቋምን በማዳከሙ የደጋፊዎቻቸውንና የተከታዮቻቸውንም ቁጥር አመናመነው:: በሌላ በኩል ደግሞ መሪዎቻቸው የነበራቸው ሥልጣንና ክብር እየተሸረሸረ በመምጣቱ አንዳንድ የሃይማኖት የኃላፊነት ቦታዎችን የሚፈልጋቸው በመጥፋቱ ክፍት ሆነው መቅረት ጀመሩ::እነዚህ እርስ በርሳቸው የተያያዙ ሁኔታዎች ቅማንቶች የአማራን ባህል የመቀበሉን እንቅስቃሴ በጣም አፋጠነው:: ይህም በመሆኑ ለዘመናት የነበራቸው የባህል ነፃነትና የውስጥ የራስ-ገዝ ሥልጣን በ1880ዎቹ ዓ.ም. ጀምሮ በአማራው አመራር እየተሸረሸረ መጣ::

የቅማንት ሃይማኖት በተግባር ላይ ሲታይ ከማኅበራዊና ከባህላዊ ዘርፎች ሥርዓት ጋር የተሳሰረ ስለነበር አረማዊ-አረታዊው የሆነው የቅማንት ዕምነት ሲተው በባህሉ ውስጥ የነበሩትን መሠረታዊ ነገሮችንና ትውፊቶችን መርሳት ግድ ሆነ:: መጠነኛ የሆነውን ክፍል ብቻ ወደ ልጁ በመተላለፉ ወደ ልጅ የልጅ ልጅ ሲወርድ ሲዋረድ ደግሞ ጭራሹን እየጠፋ ሄደ:: ባለ አንድ ዘርፍ የዘር ሐረግ አቆጣጠር እና አክራሪ ባሕርይ ከነበረው የጋብቻ ሥነ-ሥርዓታቸው ጋር የተያያዘው ጥንድ ማኅበራዊ አደረጃጀት ተረሳ፣ እንዲሁም ለቅማንት የፖለቲካና ሃይማኖታዊ አባቶች የነበረው ታማኝነት ተመናመነ:: ሴቶችን በወር አበባ ወቅታቸውና ልጅ በሚወልዱበት ጊዜ የማግለሉ ባህል ቀረ፣ ሌሎች የጎረቤት ኅብረተሰቦች የረከሱ ናቸው በማለት እንዳይቀላቀሏቸው የሚደረገው ክልከላም ተቋረጠ:: ከዚህም በስተቀር በአረማዊ-አረታዊ ሃይማኖት ሥነ-ሥርዓት መሠረት ከአንዱ የሰውነት ደረጃ ወደ ሌላው ደረጃ ለመሸጋገር የሚደረገው ሥርዓተ-ጸሎት የአንድነታቸው ጥንካሬ መሠረት የነበረ ሲሆን ይህም ወደ እያንዳንዱ ኅብረተሰብ ውስጥ ሊሠርፅ አልቻለም::

ከዚህ ቀጥሎ ለምን በርካታ ቅማንቶች በፍጥነት የአማራን ባህል በመቀበል አማራ እንደሆኑ እናያለን:: ለዚህ ጥያቄ መልሱን ለማግኘት አስቀድሞ ተመሳሳይ የሆኑ ባህላዊ መለያ ባሕርያት ለለውጥ ያላቸውን ዝግጁነትና ዝንባሌ መረዳት ያስፈልጋል:: የባህል ውህደት ሊከሰት የሚችለው ተመሳሳይ የሆኑ መሠረታዊ የባህል መለያ ባሕርይ ሲኖሩ፣ መለያ የሆኑት ባሕርይ ከነባሩ ባህል ጋር ተሳስረውና ተዋህደው በአንድ ዓይነት የባህል ዘርፍ ሊፈረጁ ሲችሉ እና ከነባሩ የባህል መለያ ባሕርይ ጋር የማይጋጩ ወይም ሁኔታውን ጨርሶ የማያከላሹ ሆነው ሲገኙ ነው:: በቅማንት ባህል ውስጥ የነበሩ ብዙ ጥንታዊ የአገው ባህላዊ ትውፊት ከአማራው ባህል ጋር ሥረ-መሠረታቸው አንድ የነበረ በመሆኑና የሚጣጣሙ ሆነው በመገኘታቸው በአማራው አቻ ባህላዊ መለያ ባሕርይ በቀላሉ ሊተኩ ችለዋል:: (ዝርዝሩ በምዕራፍ ሁለት ይገኛል)::

የመጀመሪያው የኃይል ተፅዕኖ አንድ ጊዜ ከተደረገ ወዲህ መሠረታዊ የሆነው የማኅበራዊ ድንበር የመቆጣጠሪያ ስልቶች ስለተሰበሩ አቻ የሆኑ በተመሳሳይ ባህል የሚፈረጁ የሁለቱም ሕዝቦች የባህል ትውፊቶች ስለነበሩ የቅማንቱ ባህል በአማራው

ተውጦ ውህደት ሊፈጠር ችሏል፡፡ በአገውና በአማራው በነበረው ግንኙነት ምክንያት በአንድ በኩል አንዱ የበላይ የሆነ ባህል ስለነበረው በሌላ በኩል ደግሞ የሁለቱም ባህ ሎች ተመሳሳይነት ስለነበራቸው ውህደቱ እንደተከሰተ ዓይነተኛ ምሳሌ ነው፡፡ ይህም ዓይነት የማመሣሠን ጉዳይ አረማዊ-አሬታዊ ቅዱሳንን ከክርስቲያን ቅዱሳን ጋር ከሚያመሳስሉበት ሁኔታ ጋር የተለየ አይደለም፡፡

አፄ ዮሐንስ ያወጡትን ትዕዛዝ-አዘል የባህል ለውጥ ፕሮግራም ከእሳቸው ወዲህ የመጡት ነገሥታት ትኩረት ባይሰ ጡትም ቅማንቶች የአማራውን ባህል የመቀበሉን ሁኔታ ቀጥለውበታል፡፡ የባህል ለውጡ ሂደት ቀደም ብሎ በባህል ድንበር የመቆጣጠሪያ ስልት ተገትቶ ከነበረበት ከመጀመሪያው አማራ የመሆን ሂደት በተፋጠነ መልክ በአሁኑ ጊዜ በጣም እየተጣደፈ ነው፡፡ እ.ኤ.አ. በ1930ዎቹ አብዛኛው ቅማንት ባህሉንና የማኅበረሰቡን ሥርዓት እንደያዘ ቢቆይም ወደ ክርስቲያንነት የመለወጡ ሂደት በተጠናከረ መልክ ቀጠለ፡፡ በዚያን ጊዜ በምሥራቅ ቅማንት በከርከር የሚገኙት ቅማንቶች በግምት ግማሹ ክርስትናን ተቀብለው ነበር ማለት ይቻላል፡፡ ከቅማንቱ ሃይማኖትና ባህል ሙሉ በሙሉ ባልተላቀቁት በአዲሶቹ የክርስቲያን ሃይማኖት ተከታዮች እየተረዳ አሮጌው ሥርዓት እየተንገዳገደ ቆይቶ ነበር፡፡ ምንም እንኳን ያልተጠመቁት ቅማንቶች ከክርስቲያኖች ጋር በአንድ ላይ ተቀላቅለው የቅዳሴ ሥነ-ሥርዓቶችን ባያካሂዱም ክርስቲያኖቹ ገንዘብ ማዋጣቱንና በክብረ-በዓሎች መገኘቱን አልተውም፡፡ ዛሬም ቢሆን ይህ ዓይነቱ ሁኔታ በጭልጋ ባሉት ኅብረተሰቦች ዘንድ እንደ ቀጠለ ነው፡፡

በተለይ የተለያዩ ጭንቀቶችን ለማስወገድ ወይም አካባቢያዊ ችግሮችን ለመቆጣጠር ሲፈልጉ ቅማንቶች እንደገና ወደ አሮጌው ሃይማኖታቸው ተመልሰው ልዩ ሥነ-ሥርዓታቸውን ቢያካሂዱ ከአማራው ጋር በአንዳንድ ሁኔታዎች ተመሳሳይነት ስለነበረው በአማራው በኩል የጠነከረ ተቃውሞ አይደርስባቸውም ነበር፡፡ ይህም ሊሆን የቻለው የአማራው የክርስትና ሃይማኖት አንዳንድ ጠንካራና መሠረታዊ የሆኑ አረማዊ-አሬታዊ እምነቶችን በውስጡ በማስታረቅ ያካተተ በመሆኑ ሳይሆን አልቀረም፡፡

ከጣልያን ወረራ ወዲህ እ.ኤ.አ. ከ1940 ዓ.ም. ጀምሮ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተክርስቲያን ሁለተኛውን የሃይማኖት

ማስፋፋት ዕቅድ ዘረጋች። የዚህ ዘመቻ ዋና ዓላማ በጉጣ የተከፋፈለችውን ኢትዮጵያን አንድ ለማድረግና በየጊዜው ሥርገው የሚገቡትን የውጭ ኃይሎችን ለመቋቋም እንዲያስችል ታስቦ ነበር። በዚህም መሠረት ያልተጠመቁ ቅማንቶች ርስታቸውን እንደሚነጠቁ ማስጠንቀቂያ ይደርሳቸው ጀመር። ይህ ፕሮግራም ቅማንቶችን ብቻ ሳይሆን ሌሎች በማዕከላዊ ምዕራብ ኢትዮጵያ የሚገኙትን አናሳ ጉጣዎችንም ጭምር ይመለከት ነበር። በዚያን ጊዜ እነዚህ ጉጣዎች አብዛኛዎቹ የክርስትናን ሃይማኖት ከሞላ ጎደል የተቀበሉ ቢሆንም የአማራው ባህል ግን ሙሉ በሙሉ በውስጣቸው አልሠረፀም ነበር። በዚያን ዘመን ነበር አንድ አክራሪ ሰባኪና አጥማቂ ተነሳስቶ ሁሉም ቅማንት መጠመቅ እንዳለበት በመስበኩና የተዕሰኖ እርምጃም በመውሰዱ የቅማንት በባህል ለውጥ አማራ የመሆን ሂደት ከከፍተኛው የዕድገት ደረጃ ላይ ደርሶ ወደ ፍጻሜው ደረጃ የተሸጋገረው።

## የፍጻሜው አማራ የመሆን (አምሃራይዜሽን) ሂደት

የቅማንት የአማራን ባህል የመቀበሉ ሂደት የመጨረሻው ደረጃ አሁንም ቀጥሎ እ.ኤ.አ. በ1950ዎቹ ዓ.ም. እርምጃው ተፋጠነ። በእነዚህ ዘመናት ሳይጠመቁ የቀሩት ቅማንቶች ከአንድ ሺህ በላይ አይሆኑም ነበር። በኃይልም ሆነ መሬታቸውን በመንጠቅና ጭሰኛ በማድረግ ክርስትናን እንዲቀበሉ አስገዳጅ ሁኔታዎች ቢፈጠሩም በግትርነትና በአክራሪነት እምቢተኛ የሆኑት የቅማንት የሃይማኖት መሪዎች የሚመረጡባቸው የክብርና የየታንቲ የዘር ሐረግ አባላት በእምነታቸው ፀንተው ቆዩ። በመጨረሻም እነዚህ ኅብረተሰቦች ለኢትዮጵያ መንግሥት ችግራቸውን አመልክተው ጥያቄአቸው በመንግሥት በኩል ተቀባይነት ስላገኘ ያለአንዳች እንቅፋት የሃይማኖት ነፃነታቸው እንዲጠበቅ ትዕዛዝ ተሰጥቶላቸው ነበር።

ነገር ግን የቅማንቱ ማኅበራዊና ባህላዊ ተቋም ወደፊት ምንም እንደማያዋጣ በመገንዘብ በጥቂት የሃይማኖቱ አክራሪዎች የሚደገፈው የጥንቱ የቅማንት አኗኗር ዘዴ ዘለቄታነቱ አጠራጣሪ እየሆነ መጣ። በመሆኑም የሕዝብ ብዛት ሁኔታ ከሌሎች ምክንያቶች ጋር ታክሎ የድሮው ዓይነት የቅማንት አኗኗር ዘይቤ ወደፊት እንዳይራመዱ ከማድረጉም በላይ አሮጌውን ሃይማኖት እስካሁን አጥብቀው የያዙት የዕምነቱ ተከታዮችም በኅብረተሰቡ ዘንድ ተቀባይነትና ቦታ አግኝተው ለመንቀሳቀስ ባለመቻላቸው የቅማንቱን ባህል ለመጭው ተተኪ ትውልድ ማስተላለፍ

ተሳናቸው። እንደ ሃይማኖታዊ ክብረ- በዓልን ለማክበር በርካታ ሰዎች ተገኝተው ለተለያዩ ሥርዓተ-ትዳሴዎች ለምሳሌ ተዝካር፣ የበሏግ ወቅት የልምላሜ ክብረ-በዓላት ለመሳሰሉት መዋጮ ማድረግ አስፈላጊ ከመሆኑም በላይ ለቀሳውስቱም ኑሮ አስፈላጊ የሆነውን ድጐማ መስጠት ይገባ ስለነበር ለእነዚህ መሠረታዊ ጉዳዮች መፍትሔ ባለመገኘቱ ችግሩ ተባባሰ።

ከሁሉም በላይ ደግሞ ሊወጡት ያልቻሉት ውስብስብና ጥብቅ በሆነው የጋብቻ ደንባቸው መሠረት ቴጥራቸው ከተመናመነው አረማዊ-አሪታውያን መካከል ለልጆቻቸው የትዳር ጓደኛ ማግኘት አለመቻላቸው ነበር። በዚህ ምክንያት አንድ ዝቅተኛ ቄስ ሁለት ልጃገረድ ልጆቹ ባል እንዲያገቡ ክርስትና እንዲነሱ ማድረግ ግዴታ የሆነበት ጊዜም አጋጥሟል። የወምበሩ ሚስት ሳትቀር ሴት ልጆቿ አረማዊ-አሪታዊ ሃይማኖት ተከታይ የሆኑ የትዳር ጓደኞች የማግኘት ችግር እንደሚያጋጥማቸው አሳስቧታል። ከዘመድ ጋር ተጋብቶ ግብረ-ሥጋ መፈፀም መቅሰፍት የሚያስከትል መሆኑን ስለሚያምኑ ከዚህ ለመዳን ቅማንቶች ክርስቲያን ከሆኑ ጐረቤቶቻቸው ጋር ለመጋባት በመገደዳቸው የቅማንት ኅብረተሰብ ከሃይማኖት ጋር የተያያዘው ባህል የመኖር ሕልውናው ለረዥም ጊዜ እንደማይቆይ በግልጽ እየታዩ መጣ።

እ.ኤ.አ. በ1964 ዓ.ም. አምስት መቶ ያህል አረማዊ-አሪታዊ ቅማንቶች በስምንታቸው ፀንተው የቆዩ ቢሆንም በሚቀጥሉት ሁላግ ዓመታት ጊዜ ውስጥ ሁሉም የክርስትናን ሃይማኖት ይቀበላሉ፣ ወይም ከዚህ ዓለም በሞት የሚለዩ ይሆናል። እንዲሁም ክርስቲያን የሆኑት ቅማንቶች ጥንታዊ የሆነውን አረማዊ-አሪታዊ የባህል ትውፊቶች በሚቀጥሉት አሥርተ ዓመታት ጊዜ ውስጥ በመርሳት በብዙ ሚሊዮን በሚቆጠረው የአማራው ብሔረሰብ ባህላቸው ተውጦ ጠቅላላ ውህደት እንደሚፈጠር አያጠራጥርም። በአሁኑ ጊዜ በክርስትና ሃይማኖት የተጠመቁት «ቅማንት» እየተባሉ ቢጠሩም ይህ የመታወቂያ ስም ሙሉ በሙሉ ከአማራው ጋር ሲወሃዱ የሚቀር ይሆናል። ክርስቲያን ቅማንቶች አሁንም ቢሆን የቅማንት ጐሣ አካልና የአንድ ዓይነት ስሜት ተካፋይ መሆናቸውን ያንጸባርቃሉ። በአረማዊ-አሪታዊ ቅማንቶችንና በአማራው መካከል ይታይ

የነበረው ማኅበራዊ ልዩነት በግልጽ ጉልቶ ባይታይም በአሁኑ ወቅት ክርስቲያን ቅማንቶች በመጠኑም ቢሆን ከአማራው ጋር በማኅበራዊ ኑሮ ረገድ መጠነኛ የሆነ ልዩነት አላቸው:: በባህል ግን ይህን ያህል የጎላ ልዩነት የላቸውም:: በክርስቲያን ቅማንቶችና በአማራው መካከል ያለው አነስተኛ ማኅበራዊ ልዩነት ባዕድ ያሆኑትን ሕዝቦች ከማግለል የባህል ባሕርይ የመነጨ ሳይሆን በጋብቻ ረገድ በሚያጋጥሙ ችግሮች ምክንያት ነው:: እንደሚታወቀው የቅማንት የጋብቻ ሥነሥርዓት አስቀድሞ የነበረው የዝምድና ሐርግ ተጠብቆ ስለሚፈጸም ከአጐራባች ሕብረተሰቦች የጋብቻ አቻ የማግኘቱ ዕድል የጠበበ ነው:: ሆኖም በሚቀጥሉት አጭር ዘመናት የከተሞችና የኢንዱስትሪ መስፋፋት በሚያስከትሉት ተፅዕኖ ምክንያት በጐሣ ብቻ ተወስኖ ዝግ ሆኖ የቆየው የጋብቻ ሥርዓት በቅማንት አካባቢ ሊቀጥል አይችልም፡ እንዲሁም ከዚህ ጋር ተያይዞ የነበረው አነስተኛ ማኅበራዊ ልዩነትም አብሮ እንደሚከስም ጥርጥር የለውም::

## ባሕላዊ ለውጥ በአማራነት (በአማሃራይዜሽን)

ቅማንት በአማራው ባህል ተፅዕኖ የባህል ለውጥ የተከሰተበት መሆኑን በምናነሳበት ጊዜ አንባቢያን የምዕራባዊያን ሥልጣኔ በዚህ ረገድ የተጫወተው ሚና ለምን አልተነሳም ብለው ሊገረሙ ይችላሉ:: በምዕራቡ ዓለም ተጀምሮ ዓለምን እያጥለቀለቀው ያለው የኢንዱስትሪ መስፋፋትና የከተሞች በዘመናዊ መልክ ተደራጅተው ፈጣን እድገት የማሳየታቸው ሁኔታ በቅርቡም በተመሳሳይ መልክ በመላው ኢትዮጵያ መከሰቱ የማይቀር ነው:: ነገር ግን እንደ ኢትዮጵያ በማደግ ላይ ባሉ አገሮች የኢንዱስትሪ መስፋፋት ማለት ኢንዱስትሪዎች በከተሞች ብቻ ይሰበሰባሉ ማለት አይደለም:: የኢትዮጵያ የኢንዱስትሪ ምንጭ ከአገሪቱ ርቀው በሚገኙ በሌሎች አገሮች ሊሆኑ ቢችሉም ዘመናዊ የመገናኛና የትራንስፖርት ዘዴ እየተስፋፋ ሲሄድ የኢንዱስትሪዎች መስፋፋት ተፅዕኖ የባህላዊ ለውጥን እንደሚያስከትል አይጠረጠርም:: በቅማንት አካባቢ ወደፊት ዘመናዊ ሥልጣኔ ሲስፋፋ አዳዲስ የሃብት ሥርጭትና የመገናኛ ስልት፣ ዘመናዊ የአስተዳደር ተቋሞች፣ ዘመናዊ የአስተራረስ ዘዴ እንዲሁም ዘመናዊ የትምህርትና የጤና ጥበቃ ተቋሞች ሲዘረጉና ሲቋቋሙ የነበረው የባላባታዊው የአካባቢ ራስ-ገዝ ሥርዓት አክትሞ ማዕከላዊ የሆነ ዘመናዊ አስተዳደር ይተካል የሚል እምነት አለ:: ይሁን እንጂ በያዝነው ቀሪ ዘመን የዘመናዊ

ሥልጣኔ ማስረጃ ምንጮች በአብዛኛው አውሮፓና ሰሜን አሜሪካ ሆነው ይቆያሉ።

በኢንዱስትሪ መስፋፋት ምክንያት ከተሞች እድገት ሲያሳዩ አዲስ የማኅበራዊና የባህላዊ ሥርዓተ ለውጥ በእያንዳንዱ ጉዳይ ይከሰታል። በተመሳሳይ ሁኔታ በሚደረገው የምርት ለውውጥ የዓለም ገበያ ስርጭት አካልና ተገዥ እስከመሆን ይደረሳል። ኢትዮጵያ ውስጥ ያሉትን አንዳንድ ኅብረተሰቦችን ጨምሮ በዚህ የለውጥ ሂደት ሥርዓት ምክንያት የግላዊነት መለያ ድንበራቸው እየፈራረሰ፣ ማንነታቸው እየደበዘዘ በመጨረሻም ጭራሹን ባህላቸው እንደሚዋጥ እሙን ነው።

ዘመናዊ ሥልጣኔ ከሚያስከትለው እንደዚህ ዓይነቱ ሥር-ነቀል ለውጥ አሁን ያሉት ቅማንቶችም ሆኑ ሙሉ በሙሉ በሂደት ወደ አማራነት የሚለወጡት ትውልዶቻቸው ከዚህ ሊያመልጡ አይችሉም። እስከአሁን ድረስ በእርግጥ በአለም አቀፋዊው የለውጥ ሂደት ብዙም አልተነኩም። በጣም ጥቂት የሆኑ የተፈበረኩ ቁሳቁሶች ለምሳሌ ብርጭቆ፣ የወንድ አልባሳት፣ ማንቆርቆሪያ፣ ዣንጥላና መጠነኛ የእጅ መሣሪያዎች ብቻ ናቸው በቅማንቶች ዘንድ ተሰራጭተው የሚገኙት። አመጋገባቸውም እስከአሁን ያልተለወጠና እንዲያውም ካለፉት ብዙ መቶ ዓመታት ከነበረው ሁኔታ ያልተለየ መሆኑን እንገነዘባለን። በአሁኑ ወቅት በጣት የሚቆጠሩ ቅማንቶች እርሻቸውን እየተው ጐንደር ከተማ ገብተው በመንግሥት ሥራ የተቀጠሩ አሉ። ከአንዳንድ ቤተሰብ ቁጥራቸው የተወሰነ ወጣቶች ትምህርት ቤት የገቡ ሲሆን፣ ትልቁና ዋናው ትምህርት ቤት የሚገኘው በጐንደር ከተማ ነው። ጥቂት የሆኑት ደግሞ ዘመናዊ ትምህርት አጠናቅቀው በአሁኑ ወቅት የከተማ ነዋሪዎች ሆነዋል። የመካኒክ ውጤቶችና መሣሪያዎችን በተመለከተ በአብዛኛው ቅማንት ከፈረንጆች (አውሮጳውያን) ጋር የተያያዙና በሠይጣን ኃይል እንደሚንቀሳቀሱ ነው የሚረዱት። ምንም እንኳን «የጣሊያን ሠይጣናዊ መሣሪያ እንቅስቃሾች» በከርከር አንድ የውሃ ማጠራቀሚያና አንድ የተተወ የሸክላ ፋብሪካ፣ እንዲሁም በምዕራባዊ የቅማንት አካባቢ ጠርዝ የሚሄደውን አገር አቋራጭ ጐዳና ሲሠሩ የተመለከቱ ቢሆንም ቅማንቶች በእንደኛው ፕሮጀክት እንኳን ተቀጥረው አልሠሩም፣ ከጣሊያኖችም ጋር ሆነ ከባህላቸው ጋር ተገናኝተው አልተዋወቁም።

ከኢንዱስትሪ መስፋፋት ጋር የተያያዙ የምርት ውጤቶችን ቅማንቶች የሚያገኙት ለአማራው እንደደረሱ ነው:: ኋላቀርና ባህላዊ ኅብረተሰቦች የምንላቸው በጣም ፈጣን ከሆነው የኢንዱስትሪ ከተሞች እንቅስቃሴና መስፋፋት ጋር ሳይተዋወቁ የኖሩትን ሲሆን ቅማንቶች አረማዊ-ኦሪታዊ ባህልን በመተው የኢትዮጵያ የክርስትና ሃይማኖትን ተቀብለው በባሕላዊ ሥርዓት ከመዋጥ በስተቀር ከዘመናዊው ሥልጣኔ ጋር አልተዋወቁም::

ሌሎች የኢትዮጵያ ሕዝቦች ከአማራው ሕዝብ ጋር ያደረጉትን የባህል ውህደት፣ አማራው ከቅማንትና ከሌሎች የአገው ሕዝቦች ጋር ያጋጠመውን ባህላዊ ውህደት ማነፃፀር አስፈላጊ ይሆናል:: አብዛኛው የአገው ሕዝብ ጨርሶ ሕልውናውን ረስቶ ሙሉ በሙሉ ከአማራው ጋር በመዋሃድ አማራ እስከመሆን ደረጃ የደረሰው ለዘመናት ሳይቋረጥ የእርስ በእርስ ግንኙነት የነበረ በመሆኑና የሁለቱም ሕዝቦች ባህል ተመሳሳይነት ስለነበረው ነው:: በአሁኑ ወቅት የአገው ዝርያ ከሆኑት ከቅማንቶች፣ ከፈላሻዎችና ከኩምፈሎች በስተቀር ሌሎቹ አገዎች በቡድን ለመግባባት ከሚያስችላቸው የሁለት ቋንቋ ተናጋሪ ከመሆናቸው ሌላ ጉልቶ የሚታይ የአገው ማኅበራዊና ባህላዊ ትውፊቶች የላቸውም:: የአገው ሕዝብ ቋንቋቸውን ይዘው መቆየታቸው ጉረቤቶቻቸው ከሆኑትና የበላይነትን ከያዙት የአማራና የትግሬ ሕዝቦች ጋር ደካማ የሆነ የባህል ድንበር ከመኖሩ በስተቀር አገዎችን ከሁለቱ ሕዝቦች ልዩ የሚያደርጋቸው ምንም ዓይነት ነገር እንደሌለ ነው የሚታወቀው::

በባህል ለውጥ ወደ አማራነት የመለወጡ ሂደት በተጠናከረ መልክ በአገዎች ላይ ያስመዘገበው ለውጥ በማንኛውም የሌሎች የኢትዮጵያ ብሔረሰቦች ላይ ያልደረሰና ምናልባትም ወደፊት ሊደርስ ይችላል ተብሎ የማይገመት ነው:: ዊሊያም ሻክ በጉራጌ ሕዝቦች የደረሰውን ሁኔታ ሲገልፀው «የሴም ቋንቋ ተናጋሪ የሆኑት ጉራጌዎች የአማራን ባህል በመቀበላቸው በጉራጌ አካባቢ በኢንዱስትሪ ያደጉ ከተሞች እንዲስፋፉ አላደረገም» (1666 202) :: ቀጥሎም ይህንኑ ሲያጠናክር «የአማራን ባህልና መሠረታዊ እሴት መቀበል ማለት ጉራጌዎች በአማራው ባህል በጠቅላላ እንዲዋጡ ጥርጊያ ተከፈተ ማለት አይደለም» ይላል:: (1966 203):: ከአገው ሕዝቦች ውጭ ሙሉ በሙሉ በአማራው ባህል በውህደት ለመዋጥ ተቃርበው የነበሩት በሰሜናዊ ሜፍ

የምሥራቅ የኩሽ ቋንቋ ተናጋሪዎች የነበሩት ኦሮሞዎች ናቸው:: ይህም ሊሆን የቻለው በኦሮሞዎች ፍቃደኛነት በሂደት እንጂ በማስገደድ አልነበረም:: ምንም እንኳን ኦሮሞዎች በጣልቃ ገብነት ወደዚህ አካባቢ የመጡ ቢሆንም ከአማራው ጋር የነበራቸው ለ300 ዓመታት የዘለቀው በጦርነት ጊዜ ለመተጋገዝ የገቡት ስምምነት ለኦሮሞዎች የፖለቲካና የኢኮኖሚ ጥቅሞቻቸውን ሳያስጠብቅላቸው አልቀረም::

ምንም እንኳን ሌሎች ሕዝቦች የአማራን ባህል እንዲቀበሉ ማድረጉ ከቅድመ-ኢንዱስትሪ ሥልጣኔ የመነጨ የባህል ለውጥ ክስተት መሆኑ ቢታወቅም፣ እስከአሁን ድረስ አገው ባልሆኑ ሕዝቦች በጣም አነስተኛ ተፅዕኖ ነው ያደረሰው፡ ሆኖም ወደፊት በብዙ ሕብረተሰቦች ላይ በሚቀጥሉት አሥርተ ዓመታት ለውጦች እንደሚከሰቱ አያጠራጥርም:: የአማራ ባህል ስርጭት ቀስ በቀስ በኢንዱስትሪዎች መስፋፋት እየተሻሻለ የአማራ ዝንባሌ ይዘት ያለው የኢንዱስትሪዎችና የከተሞች እድገት እንደሚከሰት ይጠበቃል:: ስለዚህ የለውጡ ሂደት በዚህ መልክ ቀጥሎ ኢንዱስትሪና ከተሞችን ማዕከል ያደረገ ቴክኖሎጂ ከተስፋፋ «ዘመናዊ» የሆነ የአማራ ባህል ከሌሎች በርካታ የኢትዮጵያ ሕዝቦች ባህሎች ጋር ውህደት ፈጥሮ የበለጠ በባህል የተሳሰረና አንድ ዓይነት አስተሳሰብ ያለው ሕዝብ የተደራጀበት አንድ አገር ለመመሥረት ያስችላል ተብሎ ይታመናል::

# ዋቢ መጻሕፍት (Bibliography)

Barnet, H.G., 1965, "Laws of Socio-Cultural Change," International Journal of Comparative Sociology, 6(2) 207-230,

Beals, Ralph, 1953, "Acculturation" In Anthropology Today, Chicago: The University of Chicago Press.

Bruce, James, 1790, "Travels to Discover the Source of the Nile in the years 1768-73", Edinburgh, G.G.I and J. Robinson.

Budge, E.A. 1928, "A History of Ethiopia," London, Methuen.

Buxton, David, 1949, "Travels in Ethiopia", New York: Mc - Bride

Cerulli, Ernesta, 1956, "Peoples of South-West Ethiopia and its Borderland",London.

Cheesman, Robert E, 1936, Lake Tana and the Blue Nile, An Abyssinian Quest, New York: Macmillan.

Clark, J. Desmond, 1954, "The Prehistoric Cultures of the Horn of Africa", NewYork:Cambridge.

Consociazione Turistica Italiana, 1938, "Guida de Africa Oriental Italiana. Milan: Consociazione Turistica Italiana

Conti Rossini, Carlo, 1912, "La Langue des Kemant en Abyssinie"

Doresse, Jean, 1959, "Ethiopia" London: Elek Books.

Flad, Johnson M.A., 1866, "A Short Description of the Falashas and Kemant in Abyssinia" Chrishona: The Mission Press.

Gamst, Frederick C., 1965, "Travel The Mission Press and Research in Northwestern Ethiopia. "Addis Abeba" Institute of Ethiopia Studies.

Gobat, Samuel, 1834, "Journal of a three years' in Abyssinia. "London Hatchard & Son

Greenberg, Joseph H., "The Lanquages of Africa" International Journal of American Linguistics.

Halévy,J., 1877, "Travels in Abyssinia" London: A.L. Lowey.

Heuglin, Martin T.Von., 1868, "Reise nach, Jena: Abessinien"

Huntingtord, G.W.B.,"The Galla of Ethiopia." London: International Af. Institute

Jager,Otto A 1965 "Antiquities of North Ethiopia"
Stuttgart F A .Brockhaus
Leiris, Michel, 1958, "La Possession et ses Aspects Theatraux chez les Ethiopians de Gondar" Paris: Librairie Plon
Leroy, Jules, S.Wright and O.A. Jager, 1961 Ethiopia "Illuminated Manuscripts"., Greenwich, Conn.
Leslau, Wolf, 1951, "Falasha Anthology". New Haven: Yale University Press.
Levine, Donald N.1965, Wax and Gold "Tradition and Innoviation in Ethiopia, Culture" New Haven: Yale University Press.
Lewis, Herbert S., 1965, "A Galla Monarchy - Jimma Aba Jifar Ethiopia, 1930-1932", Madison University of Wisconsin Press.
Lewis, I.M. 1955, "People of the Horn of Africa, Somali, Afar and Saho, London International Africa Institute
Murdock, George P., 1949, "Social Structure", New York: Macmillan.
Messing, Simon D, 1958 "Group Therapy and Social Status in the Zar Cult of Ethiopia" American Anthropologist.
Pankhurst, Richard, 1961 "An Introduction to the Economic History of Ethiopia"., London: Lalibela House.
Perham, Margery. "The Government of Ethiopia",-London: Fabor.
Rassam, Hormuzd, 1869, "Narative of the British Mission to Theodore, King of Abyssinia", London: J. Murray, 2vols.
Rathjens, Carl, 1921, "DieJuden in Abessinien." Hamburg
Ruppel Edward, 1838-1840, "Reise in Abessinien", Framkfurt.
Sahile Silassie, 1964, Shineg Village, Scene of Ethiopia Life," Wolf Leslan,Translations. Berkeley.
Shack, William A., 1966, "The Gurage: Peoples of Ensete Culture," London: Oxford
Simoons, Frederick J, 1960, "Northwest Ethiopia, Peoples and Economy," Madison University of Wisconsin Press.
Stern, Henry A, 1862, "Wanderings among the Falashas in Abyssinia," London:Wertheim, Macintosh, and Hunt.

Trimingham, J. Spencer, 1965, "Islam in Ethiopia" London:Frank Cass & Co.

Rubiana, Joseph, 1959, "Note sur la Distribution Geographique des Dialects Agaw ", Inmer Rouge-Afrique Orientale.

Tucker, Archibald N. and M.A. Bryan 1966", Linguistic Analysis: the non-Bantu Languages of North Eastern Africa," London: Oxford.

Ullendorff, Edward, 1956, "The Hebraic - Jewish Elements in Abyssinian (Monophysite) Christianity", Journal of Semetics Studies, New York: Oxford.



ተርጓሚው አቶ ባዩ ቦጋለ ላቀው

አቶ ባዩ ቦጋለ ላቀው በ1932 ዓ.ም. በጐንደር ከተማ አጠገብ ተወለዱ:: በ1956 ዓ.ም. ከአዲስ አበባ ዩኒቨርስቲ በፖብሊክ አድሚኒስትሬሽን ናቢ.ኤ. ዲግሪያቸውን ካገኙ በኋላ በተለያዩ የመንግሥት መሥሪያ ቤቶችና ድርጅቶች ከክፍል ሹምነት ጀምሮ እስከ መምሪያ ኃላፊነት በሚደርሱ የሥራ ኃላፊነት ለ29 ዓመት ያህል ለአገራቸው አገልግሎት አበርክተዋል::

አታሚው፡ ብርሃንና ሰላም ማተሚያ ድርጅት

ዋጋ:በአገር ውስጥ ብር 20.00
በውጭ አገር ዩ.ኤስ. $ 12.00 (ከመላኪያ ጋር)